# ምዕራፍ ፪

## ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ

የወልደጊዮርጊስ አባት አቶ ወልደዮሐንስ ናዳቸው ትውልዳቸው ከቡልጋ ሲሆን፣ እናታቸው ወይዘሮ ወደርየለሽ ወልደገብርኤል ደግሞ የመንዝ ተወላጅ ናቸው።

አቶ ወልደዮሐንስ ጊዜው መቼ እንደሆነ በትክክል ባይታወቅም፣ በወጣትነት ዘመናቸው ተወልደው ካደጉበት ከቡልጋ ወደ አዲስ አበባ መጥተው፣ ቀድሞ አባታችን ሠፈር እየተባለ በሚጠራው በቅድስት ማርያም ቤተክርስቲያን አካባቢ፣ የዝናር ስፌትና የበቅሎ ዕቃዎች ዝግጅት የሞያ ሥራ አቋቁመው ይተዳደሩ ነበር። ወይዘሮ ወደርየለሽ ደግሞ ከአገራቸው ከመንዝ ወደ ሐረርጌ በመዛወር፣ ከራስ መኰንን ጭፍሮች አንዱን አግብተው አንድ ወንድና አንዲት ሴት ልጅ ከወለዱ በኋላ፣ ባለቤታቸው በድንገት ሲሞቱባቸው፣ አገሩን ለቅቀው ወደ አዲስ አበባ መጡ።

ወይዘሮ ወደርየለሽ በአዲስ አበባ አባታችን ሠፈር ቅድስት ማርያም ቤተክርስቲን አካባቢ በሚገኘው በዘመዶቻቸው ቤት መኖር እንደጀመሩ፣ ጐረቤታቸው ከሆኑት ከአቶ ወልደዮሐንስ ጋር ተዋውቀው፣ ጋብቻቸውን በፈጸሙ በዓመቱ አንድ ወንድ ልጅ ወለዱ። ስሙንም "ወልደጊዮርጊስ" ብለው ሠየሙት። ወልደጊዮርጊስ ለእናቱ ለወደርየለሽ ሦስተኛ ልጅ ሲሆን፣ ለአባቱ ለወልደዮሐንስ የመጀመሪያ ወንድ ልጅ ሆነ።

አቶ ወልደዮሐንስ ከወይዘሮ ወደርየለሽ ጋር በመሠረቱት የጋብቻ ሕይወትና ከአንድ ዓመት በኋላ ባፈሩት ወንድ ልጅ ከፍ ያለ ደስታ ከማግኘታቸውም በላይ፣ በራሳቸው ብርታትና ጥረት ያቋቋሙት የዝናር ስፌትና የበቅሎ ዕቃዎች ምርት ተፈላጊነታቸው እየጨመረ በመሄዱ፣ ትዳራቸውንና ንብረታቸውን ለማሻሻል አስችሏቸዋል። በዚህ አኳኋን የሞያው ሥራ እየተስፋፋና ገቢያቸውም እየዳበረ በመሄዱ፣ ቀበና ዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል አጠገብ ሰፋ ያለ ቦታ በመግዛት፣ ለመኖሪያቸውና ለሥራቸው የሚበቃ ሰፊ ቤት ከሠሩ በኋላ፣ ከኪራይ ቤት ወጥተው የራሳቸው በሆነ ንብረት የተሻለና የተመቻቸ ሕይወት ለማግኘት ቻሉ።

አቶ ወልደዮሐንስ ከሚወዷቸው ባለቤታቸው ከወይዘሮ ወደርየለሽ ያፈሩት ልጅ ዕድሜው ለትምህርት ሲደርስ፣ በአዲስ አበባ በቅድስት ሥላሴ ቤተክርስቲያን ቅጥር ግቢ በሚገኘው ትምህርት ቤት የአማርኛን ጽሕፈትና ንባብ እንዲማር አስገቡት። ሕፃኑ ወልደጊዮርጊስ ለቀለም ትምህርት የተዘጋጀ ብሩህ አእምሮ ያለው በመሆኑ፣ ፊደል ከመቁጠር ተነሥቶ በጥቂት ዓመታት ውስጥ ዳዊት ደገመ። ከዚያም ግዕዝንና ትርጓሜውን በሚያጠናበት ጊዜ፣ አስተማሪዎቹ ትጋቱንና ትምህርት የመቅሰም ፍጥነቱን በማየት፣ ወደ ሌላ ቦታ ለምሳሌ ወደ እንጦጦ ማርያም ወይም ወደ ራጉኤል ተልኮ፣ ዜማና ቅኔ ቢማር እንዴት ያለው ሊቅ ይወጣው ነበር? እያሉ አስተያየት መስጠት ጀመሩ።

ወጣቱ ወልደጊዮርጊስ ግን፤ የእሱ ዕድሜ እኩያ የሆኑት አንዳንድ ልጆች ያገኙትን ዕድል በማየት፤ ዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ገብቶ ዘመናዊውን የውጭ አገር ትምህርት ለመማር ጽኑ ፍላጐት አደረበት። እዚህ ላይ ወላጆቹ ሁለት ሐሳብ ላይ ወደቁ። አንደኛ በዘመኑ በነበረው አስተሳሰብ የፈረንጅ ትምህርት የሚማሩ ልጆች፤ አስተማሪዎቻቸው እያታለሏቸው ሃይማኖታቸውን ያስለውጧቸዋል በሚል ሥጋት የልጃቸውን ፍላጐት አንቀበልም የሚል ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ የሥላሴ ቤተክርስቲያን አስተማሪዎች እንዳሳሰቡት፤ ለአገር ባሕል ትምህርት፤ የሚወዱት ልጃቸው ከእነሱ ተለይቶ ብቻውን ወደ ሌላ ሩቅ ቦታ እንዲሄድባቸው አለመፈለግ ነበር። እንግዲህ ምን ይሻላል? ከአቶወልደዮሐንስ ወዳጆች አንዳንዶቹ፤ ወልደጊዮርጊስ አማርኛን ጠንቅቆ ማወቅ ብቻ ሳይሆን፤ ሲጽፍ ብዕሩም የተስተካከለ በመሆኑ፤ እዚሁ አዲስ አበባ በአንድ መሥሪያ ቤት ውስጥ የጽሕፈት ሥራ ቢፈለግለት ይሻላል የሚል ሐሳብ ሲሰጡ፤ ሌሎች ደግሞ ይህንን በመሳፍንቱና በመኳንንቱ ዘንድ እጅግ የተደነቀውን የአባቱን የእጅ ሥራ ሞያ ቢቀጥል ምን አለበት? የሚሉ ነበሩ። ለዚያም ሆነ ለዚህ፤ ወጣቱ ወልደጊዮርጊስ ከልቡ የቆረጠበትን ሐሳብ የሚለውጥ አልሆነም። የእርሱ ቁርጠኛ ፍላጐት፤ ዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ገብቶ ዘመናዊውን የውጭ አገር ትምህርት መማር ብቻ ነው። ይህንንም ሐሳቡን ወላጆቹ ስላልተቀበሉለት፤ በተፈጥሮ ካለው የኃይለኛነት ጠባይ ጋር እጅግ ቅብጥብጥና ቁጡ እየሆነ ቤተሰቡን በማስቸገር ብዙ ቆየ።

በመጨረሻው አንድ ከቤተሰቡ ጋር ዝምድና ያላቸው ነጋድራስ መንግሥቱ አየለ የተባሉ ሰው፤ የውጭ አገር ትምህርት በመጠኑ የተማሩና በሥራም ጅቡቲ የኖሩ በመሆናቸው፤ አቶ ወልደዮሐንስንና ወይዘሮ ወደርየለሽን መክረው፤ ወጣቱ ወልደጊዮርጊስ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ገብቶ ፈረንሣዊኛ እንዲማር አስደረጉ። የዘመኑን ሥልጣኔ የቀመሱት ነጋድራስ መንግሥቱ፤ ባሕልና ወግ አጥባቂ የሆኑትን አቶ ወልደዮሐንስንና ወይዘሮ ወደርየለሽን፤ ፈረንሣይኛ ወይም እንግሊዝኛ መማር ጥቅሙ ምን እንደሆነ ለማስረዳትና በተለይም የውጭ አገር ትምህርት በማጥናት ሃይማኖትን የሚያስለውጥ አንዳች ነገር አለመኖሩን ለማሳመን በብዙ ደክመዋል።

ወጣቱ ወልደጊዮርጊስ የውጭ አገር ትምህርት ለመማር እንዲችል ወላጆቹ የሚፈቅዱለትን ቀን ተስፋ ሳይቆርጥ ሲጠባበቅ ብዙ የትምህርት ዓመታት ቢቃጠሉበትም፤ በነጋድራስ መንግሥቱ ብርታት፤ ዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ከገባ በኋላ ፈረንሣዊኛ በመማር የመጀመሪያውን ደረጃ በ1912 ዓ.ም በተወለደ በአሥራ ዘጠኝ ዓመቱ በጥሩ ውጤት ፈጸመ። ይሁን እንጂ የወጣቱ ፍላጐት በዚህ ብቻ ተወስኖ ለመቅረት አልነበረም። ዕድል ቢያገኝ ወደ ፈረንጅ አገር ተልኮ ከፍተኛ ትምህርት ለመቀጠል ጥልቅ ምኞቱ ነበር። ነገር ግን፤ በዚያን ዘመን ራስ ተፈሪ መኰንን የኢትዮጵያ መንግሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ ከሆኑ ሦስተኛው ዓመት ላይ ስለሆኑ፤ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት የፈጸሙትን ወጣቶች ሁሉ ወደ ፈረንጅ አገር ለመላክ የተዘጋጁበት ጊዜ አልነበረም። ታሪኩ እንደሚነግረን፤ አልጋወራሽ ተፈሪ ከዳግማዊ ምኒልክና ኋላም ራሳቸው ካቋቋሙት ከተፈሪ መኰንን ተማሪ ቤት፤ በፈረንሣዊኛ ወይም በእንግሊዝኛ የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት የፈጸሙትን ወጣቶች ወደ ውጭ አገር በብዛት መላክ የጀመሩት ከኅዳር 21 ቀን 1919 ዓ.ም ጀምሮ ነው። ከዚህ ጊዜ በፊት በተለይም ከ1914 ዓ.ም ጀምሮ በየዓመቱ በጣት የሚቆጠሩ ጥቂቶች ተማሪዎች ወደ ፈረንጅ አገር ለመላክ የተቻለው፤ ራስ ተፈሪ ከአንዳንድ የውጭ አገር በጐ አድራጊዎች ጋር ተነጋግረው በተገኘው እርዳታ እንጂ፤ በትምህርት

ሚኒስቴር መደበኛ በጀት አልነበረም። ይህንንም ዕድል ካገኙት ወጣቶች መካከል፤ ሎሬንሶ ታዕዛዝ፣ መላኩ በያን፣ በሻህ ውረድ ሀብተወልድ፣ ወርቁ ጉበና፣ አንዳርጋቸው መሣይና ዘውዴ በላይነህ ይገኙበታል።

ስለዚህ በ1912 ዓ.ም በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርታቸውን የፈጸሙት፤ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፣ መታፈሪያ ወልዴና አበበ ወንድምአገኘሁ የተባሉት ሦስት ወጣቶች፤ ወደ ፈረንጅ አገር የመሄድ ዕድል ባይኖራቸውም፤ በአዲስ አበባ የፈጸሙት ትምህርት የተከበረ በመሆኑ፤ በንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱና በአልጋወራሽ ራስ ተፈሪ መኰንን መልካም ፈቃድ፤ ሰኔ 4 ቀን 1912 ዓ.ም በጉምሩክ መሥሪያ ቤት ተቆጣጣሪዎች (ኢንስፔክተሮች) ሆነው እንዲሠሩ በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ ተመደቡ።

እነዚህ ሦስት ወጣቶች የተሰጣቸውን ኃላፊነት እንደጀመሩ፤ ከመካከላቸው አንዱ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በተሰጣቸው ሥራ የማይደሰቱ ሆኑ። በዚያን ዘመን በንግሥተ ነገሥታት ዘውዲቱ ማህተም የመንግሥት ሠራተኛ መሆን፤ በተለይም የጉምሩክ ኢንስፔክተር መባልና ደህና የመተዳደሪያ ደሞዝ ማግኘት፤ ማንም ሰው በቀላሉ የሚያገኘው ዕድል አለመሆኑን ወልደጊዮርጊስ ተረድተውታል። ነገር ግን ያንን የጀመሩትን ፈረንሣዊኛ የበለጠ ለማስፋፋትና ብዙ መጻሕፍቶችን በማንበብ፤ የዘመኑን ሥልጣኔ ለመከታተል የሚያስችል ዕውቀት ለማግኘት፤ የጉምሩክ መሥሪያ ቤት ምንም ዓይነት ዕድል እንደማይከፍትላቸው ስለተገነዘቡ፤ ሌላ ሥራ መፈለግ ይሻለኛል አሉ። የሚመኙትም ሥራ በፈረንሣዊኛ የሚሠራበት፤ ቢቻል በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር፤ ባይሆን ደግሞ በፈረንሣይና በኢትዮጵያ የምድር ባቡር ኩባንያ ስለነበረ፤ ለሁለቱም መሥሪያ ቤቶች የሚያማልዳቸውና የሚረዳቸው ዘመድ ሳያገኙ ቀሩ። በመጨረሻው በራሳቸው ጥረት ሥራ ሲያፈላልጉ፤ በዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል ለሚያክሙት ፈረንሣዊኛ ተናጋሪ ለሆኑት የውጭ አገር ሐኪሞች አስተርጓሚ የሚሆን ሰው ለመቅጠር ክፍት ቦታ መኖሩን ሰሙ። ለዚህ ሥራ ወልደጊዮርጊስ ወዲያውኑ አመልክተው ፈተናውን እንዳለፉ፤ በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ የተሾሙትን የጉምሩክ ተቆጣጣሪነት ሥራ አልፈልግም ብለው ለቀቁ።

በዚያን ዘመን በነበረው የአስተሳሰብና የአሠራር ሁኔታ፤ አንድ ሰው በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ የተሰጠውን ሥራ፤ ሲያመቸው አልፈልግም ብሎ መልቀቅ ይችል ኖርዋል ወይ? ተብሎ ለሚቀርበው ጥያቄ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ምርምር ሲያደርግ ሁለት ዓይነት አስተያየቶች አግኝቷል። ወልደጊዮርጊስ የጉምሩክ ሥራቸውን ለቅቀው የወጡት፤ ኃይለኛ በሆነው ጠባያቸው የኢንስፔክተር ተግባር የኃላፊዎቹን ሥራ ሁሉ ለመቆጣጠር የሚያስችል ነው ብለው በፈጠሩት ችግር፣ ዋናው ዲሬክተር ተንኮል ፈልጉ ከሥራ ስለአገዳቸው ነው የሚል ሲሆን፤ ሌላው ደግሞ ወልደጊዮርጊስ ፈረንሣዊኛቸውን ለማስፋፋት ባደረባቸው ጽኑ ፍላጎት ወደ አስተርጓሚነት ሥራ ለመዛወር የቻሉት፤ የጉምሩኩን ዋና ዲሬክተር ድጋፍ አግኝተው ነው የሚል ነበር። ይህን ሁለተኛውን አስተያየት እጅግ ወደ እውነቱ የተቃረበ አድርገው የሚያምኑት ብዙዎች ናቸው። ከነዚህም መካከል ወልደጊዮርጊስን በሥራ ዓለም የሚያውቋቸው፤ ቢትወደድ ዘውዴ ገብረሕይወት፣ ቀኛዝማች ፈለቀ እርገቱ፣ ብርጋዲየር ዤኔራል መኰንን ደነቀ ይገኙበታል። በተለይም የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ በመሆን ትልቁን ማሕተም ይዘው ለብዙ ዓመታት የሠሩት ቀኛዝማች ፈለቀ እርገቱ እንደገለጹልኝ፤ አንድ ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ስለልጅነታቸው ታሪክ እንሥተው ሲያጫውቷቸው፤

" ... በጽሕፈት ሚኒስቴር ማዘዣ የተሾምኩበትን የጉምሩክ ተቆጣጣሪነትን ለቅቄ የሐኪሞች አስተርጓሚነትን ሥራ የመረጥኩበት ምክንያት፤ በፈረንሣዊኛ ቋንቋ ለመግፋትና ከዚያም ቢቻል ወደ ውጭ አገር ሄዶ የመማር ዕድል አገኝ ይሆናል በሚል ተስፋ ነበር ... " ብለው የነገሯቸውን ቀኛዝማች ፈለቀ በትክክል ያስታውሳሉ። ከዚህ ውጭ ግን፤ ወልደጊዮርጊስ ከጉምሩክ መሥሪያ ቤት የለቀቁት ምን ያህል ጊዜ ከሠሩ በኋላ እንደሆነ፤ ቀጥሎም ዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል የአስተርጓሚነት ሥራቸውን የጀመሩት መቼ መሆኑን ቀኛዝማች ማወቅ አልቻሉም። በዘመኑ በነበረው አሠራር የጉምሩክ መሥሪያ ቤት የሚታዘዘው በንግድ ሚኒስቴር ሲሆን፤ የዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል ደግሞ የሚተዳደረው በአገር ግዛት ሚኒስቴር ነበር። በዚህ መሠረት በተደረገው ምርምር፤ የወልደጊዮርጊስ የጉምሩክ ተቆጣጣሪነት ሥራ ለምን ያህል ጊዜ እንደቆየ ትክክለኛውን ቀንና ዓመተ ምሕረት ለማወቅ አልተቻለም። ይሁን እንጂ በተገኘው መረጃ፤ ወልደጊዮርጊስ በ1912 ዓ.ም ጉምሩክ የገቡት በሹመት እንደነበረና፤ ከዚያም ለቅቀው ዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል በፈረንሣይኛ አስተርጓሚነት በመቀጠር እስከ 1920 ዓ.ም ድረስ ማገልገላቸው የተረጋገጠ ሆኗል።

## ከአስተርጓሚነት ወደ ዲፕሎማትነት

ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል በሚሠሩበት ጊዜ፤ በመስከረም 1919 ዓ.ም ከአንድ የመንግሥት ከፍተኛ ባለሥልጣን ጋር ተዋወቁ። እኚህም ባለሥልጣን ከ1917 ዓ.ም ጀምሮ የአልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን መንግሥት የእርሻና የመሥሪያ ሚኒስቴር* ዋና ዲሬክተር የሆኑት አቶ መኰንን ሀብተወልድ ናቸው። በዚያን ጊዜ ዋና ዲሬክተር የተባለው ሹመት፤ ከሚኒስትሩ ቀጥሎ እንደ ምክትል ሚኒስትር፤ የሚኒስቴሩን ልዩ ልዩ የሥራ ክፍሎች እያስተባበረ የሚመራ ማለት ነው።

አቶ መኰንን ሀብተወልድ ከልጅነታቸው ጀምሮ በተለይ በብርድ ወራት የአስም ሕመም ስለሚያጠቃቸው፤ በየጊዜው ሕክምና ይደረግላቸው ነበር። የ1919 ዓ.ም ዘመን እንደተጀመረ፤ አቶ መኰንን ይህ አብሮአቸው የቆየው የአስም ሕመማቸው ከወትሮው የበለጠ ስለአስቸገራቸው፤ በምኒልክ ሆስፒታል ተኝተው ለረዥም ጊዜ እንዲታከሙ ሐኪሞቹ ወሰኑ። በዚህ ጊዜ የሐኪሞቹ አስተርጓሚ የሆኑት አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከሚጠበቀው በላይ ደስ የሚያሰኝ እርዳታ አደረጉላቸው። ይኸውም፤ ሐኪሞቹ መርምረው የደረሱበትን የሕመማቸውን ሁኔታና፤ ከዚህም ለመዳን በየዕለቱና በየሰዓቱ የሚወስዷቸውን መድኃኒቶች ለበሽተኛው አጣርቶ በማስረዳት፤ ሕመምተኛውም በበኩላቸው ሕክምናቸውን ከጀመሩበት ቀን እንሥቶ በየዕለቱ የሚሰማቸውን፤ ሐኪሞቹ እንዲያውቁት በማድረግ ነበር። ከዚህም በቀር አቶ ወልደጊዮርጊስ በሽተኛውን በየሰዓቱ በመጠየቅ፤ ሐኪሞቹም የሰጡትን ተስፋ እየነገሩ በማጽናናት በሚሰጧቸው እርዳታ፤ መኰንን ሀብተወልድ ከፍ ያለ የባለውለተኛነት ስሜት አደረባቸው።

በመሠረቱ በሁለቱ ሰዎች መካከል የዕድሜም የሥልጣንም ልዩነት ስለአለ፤ በዚያ በሆስፒታል የሕይወት ዘመን ምንም ቢተሳሰቡና ቢግባቡም፤ ጓደኛሞች ለመሆን የሚችሉበት ጊዜ አልነበረም። መኰንን ሀብተወልድ ወልደጊዮርጊስን

---

* በአሁኑ አነጋገር የእርሻና የሥራ ሚኒስቴር ማለት ነው።



የአቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ቤተሰቦች፤

ከግራ ወደ ቀኝ ወ/ሮ ወደርየለሽ ወ/ገብርኤል፣ አቶ ወልደዮሐንስ ናዳቸው፣ የወልደጊዮርጊስ ባለቤት ወ/ሮ የክትነሽ ወ/ማርያም ሲሆኑ፤ በስተጀርባ አቶ ሞገስ ወልደዮሐንስ፣ አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ እና አቶ መኰንን ወልደዮሐንስ ይታያሉ፤

በዕድሜ ሰባት ዓመት ይበልጣሉ። በመንግሥት ሥራም ከፍተኛ ሥልጣን ላይ የደረሱ ከመሆናቸውም በላይ፣ የአልጋወራሽ ተፈሪ መኰንን ልዩ ባለሟል ናቸው ተብሎ ዝናቸው በሰፊው የታወቀ ነው። ሕመምተኛው መኰንን አንድ ጠዋት በጣም ተሽሏቸው ደስታ በተሰማቸው ሰዓት፣ ከአቶ ወልደጊዮርጊስ ጋር የሚከተለውን ውይይት አደረጉ።

መኰንን ሀ.ወ ወንድሜ የየት አገር ሰው ነህ?

ወልደጊዮርጊስ በእናቴ መንዝ በአባቴ ቡልጋ ነኝ።

መኰንን ሀ.ወ ይገርማል! እኔ ደግሞ በአባቴ መንዝ በእናቴ ቡልጋ ነኝ። የት ተወልደህ አደግህ?

ወልደጊዮርጊስ፣ የተወለድኩት እዚሁ አዲስ አበባ አባታችን ሠፈር ነው። ያደግሁትም በዚሁ አካባቢ ነው።

መኰንን ሀ.ወ፣ ይህን አቀላጥፈህ የምትናገረውን ፈረንሣዊኛ የት ነው የተማርከው? ለመማርስ ስንት ዓመት ፈጀብህ?

ወልደጊዮርጊስ፣ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት ለአምስት ዓመታት በፈረንሣዊኛ የሚሰጠውን የመጀመሪያውን ደረጃ ትምህርት ፈጽሜአለሁ። ከዚያም በአልጋወራሽ ተፈሪ ፈቃድ በጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት ተቆጣጣሪ ሆኜ እንድሠራ ተመድቤ ነበር። እኔ ግን ፈረንሣይኛዬን የበለጠ ለማሻሻል እንዲረዳኝ፣ በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርና በምድር ባቡር ኩባንያ ሥራ ለማግኘት ሞክሬ ሳይሳካልኝ ስለቀረ፣ እዚህ ሆስፒታል ለሐኪሞቹ አስተርጓሚና ረዳት ሆኜ ስሠራ አምስት ዓመት ሆኖኛል።

መኰንን ሀ.ወ፣ ታዲያ አሁን ባለህበት ሥራ ለትምህርቱም ለኑሮህም የሚሻል ሆነልህ ወይ?

ወልደጊዮርጊስ፣ ዘወትር በፈረንሣዊኛ በመነጋገር ችሎታዬን ለማሻሻል በጣም ረድቶኛል። ከዚህ በላይ ደግሞ ብዙ ታማሚዎች እዚህ እየመጡ ሕመማቸውን ለሐኪሞቹ ለማስረዳት ስለሚቸገሩ፣ እነሱን ለመርዳት በመቻሌ ደስ ብሎኛል። በኑሮ በኩል ግን እንደሚያውቁት የሆስፒታል ሠራተኛ የሚያገኘው ደሞዝ ይህን ያህል ኑሮን የሚያመቻች አይደለም።

መኰንን ሀ.ወ፣ የተናገርከው ትክክል ነው። እኔ አንተ ላይ ሁለት ማስፈያ ነገሮች አያለሁ። የመጀመሪያው ችሎታህና ቅልጥፍናህ ነው። ሁለተኛው በሽተኛን ለመርዳት ከመንገድህ እየወጣህ የምታደርገው ቅንነት ነው። እኔ ልንገርህ! ፈረንሣዊኛ በአሊያንስ ፍራንሴዝ ማታ ማታ ለጥቂት ዓመት አጥንቼ እንደ አቅሜ ትንሽ እናገራለሁ። ነገር ግን እንደ አንተ የማስበውን ሁሉ አቀላጥፌ መግለጥ አልችልም። ሆኖም ጥናቴን አሁንም አላቋረጥኩም። ወደፊትም እቀጥላለሁ። አንተ ግን በዳግማዊ

ምኒልክ ተማሪ ቤት መደበኛ ተማሪ ሆነህ በመማርህ፣ ማለፊያ መሠረት ጨብጠሃል። እንዳልከው አሁንም ከሐኪሞች ጋር መሥራትህ ጠቅሞሃል። ቀደም ሲል እንደተመኘኸው በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ተቀጥረህ ፈረንጆችን በሚመለከት ጉዳይ በፈረንሣዊኛ ቋንቋ እንድትሠራ ቢደረግ፣ አገርህንም ትጠቅማለህ፣ አንተም በሥራ ታድጋለህ ብዬ አስባለሁ። ምን ይመስልሃል?

ወልደጊዮርጊስ፣ ቀደም ብዬ እንደገለጽኩልዎ፣ ሥራ ለመሥራት የፈለግኩትና የሞከርኩት በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ነበር። በዚያን ጊዜ ችሎታዬን መዝኖ ወደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የሚያቀርበኝ አላገኘሁም። አሁን እርስዎ የሚቻል መስሎ ከታይዎ፣ በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ለመሥራት በጣም ደስ ይለኛል።

መኰንን ሀ.ወ፣ በል እንግዲህ የተነጋገርነው ሁሉ በልባችን ይቆይ! በዚሁ ሆስፒታል በምቆይበት ሰሞን የሚቻለውን አድርጌ እነግርሃለሁ።

የአቶ መኰንን ሀብተወልድና የአቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የመጀመሪያው ቀን ውይይት እዚህ ላይ ይቆማል።

ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ "የእርሻና የመሥሪያ ሚኒስቴር"* ዋና ዲሬክተር የቤተ መንግሥቱ ልዩ ባለሟል በመሆናቸው፣ በዳግማዊ ምኒልክ ሆስፒታል ለሁለት ወራት ተኝተው ሲታከሙ፣ ንግሥቲቱ ከአንድም ሁለት ጊዜ፣ አልጋወራሹ ደግሞ ቢያንስ በሳምንት አንድ ጊዜ እየተመላለሱ ይጠይቋቸው ነበር።

አንድ ቀን አልጋወራሽ ተፈሪ ሊጠይቋቸው በመጡ ጊዜ ሁኔታው የሚያመች ሆኖ ሲያገኙት፣ መኰንን ሀብተወልድ የወጣቱን የወልደጊዮርጊስን ጉዳይ አነሡ።

መኰንን ሀ.ወ፣ ልዑል ጌታዬ ቢፈቅዱልኝ እዚህ ሆስፒታል በምታከምበት ጊዜ፣ የሐኪሞቹ አስተርጓሚ ሆኖ የሚሠራ፣ ፈረንሣዊኛ በጣም ጥሩ አድርጎ የሚናገር፣ ቅንነትና ብልህነት ያለው አንድ ልጅ አይቼ በጣም ተደንቄያለሁ።

ራስ ተፈሪ፣ ታዲያስ?

መኰንን ሀ.ወ፣ እኔ እንዳየሁት ይህን የመሰለ ችሎታ ያለውና ቀልጣፋ የሆነ ልጅ በዚህ ሆስፒታል በቱርጆማንነት (አስተርጓሚነት) ጊዜውን ከመግፋት፣ ወደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ቢዛወር ለመንግሥት በጣም ጠቃሚ የሆነ አገልግሎት እንደሚሰጥ ከልቤ አምኛለሁ። ለማናቸውም ልዑል ጌታዬ ፈቃድዎ ቢሆን አሁን ተጠርቶ ቢያነጋግሩት የተገባ ይመስለኛል።

* የእርሻና የሥራ ሚኒስቴር ማለት ነው።

አልጋ ወራሽ ተፈሪ መልካም ፈቃዳቸው ይሆንና ወልደጊዮርጊስ ተጠርቶ መጥቶ እጅ ይነሣል፡፡

አልጋወራሽ፤ ፈረንሣዊኛ የት ነው የተማርከው?

ወልደጊዮርጊስ፤ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት የሚሰጠውን የመጀመሪያ ደረጃ ትምህርት አጠናቅቄያለሁ፡፡

አልጋወራሽ፤ ከዚያስ በኋላ?

ወልደጊዮርጊስ፤ ዕድሜ ለልዑል አልጋወራሽ! አንዳንድ ወገኖቼ ዕድል እንዳገኙት እኔም ውጭ አገር ተልኬ ለመማር ብርቱ ምኞት ነበረኝ፡፡ በዚያን ጊዜ ዕድሉ ስላልተገኘ፤ በልዑልነትም መልካም ፈቃድ ከሌሎች ጓደኞቼ ጋር በጉምሩክ ዋና መሥሪያ ቤት ተቆጣጣሪ ሆኜ እንድሠራ በጽሕፈት ሚኒስቴር ተመድቤ ነበር፡፡ ነገር ግን፤ በተማሪ ቤት ያገኘሁትን የፈረንሣይኛ ዕውቀት በቃል ንግግርም ሆነ በጽሑፍ ለማሻሻል እንዲረዳኝ፤ እዚህ ሆስፒታል ለሐኪሞቹ አስተርጓሚ ሆኜ ስሠራ አምስት ዓመት ሆነኝ፡፡

አልጋወራሽ፤ ታዲያ አሁን ምን እንድናደርግልህ ትፈልጋለህ?

ወልደጊዮርጊስ፤ የእኔ የመጀመሪያ ምኞቴ፤ ወደ ውጭ አገር ተልኬ የመማር ዕድል ማግኘት ነበር፡፡

አልጋወራሽ፤ ዕድሜህ ስንት ሆኗል?

ወልደጊዮርጊስ፤ ሐያ ስድስት ዓመቴ ነው፡፡ እርግጥ የትምህርት ዕድሜህ ትንሽ ተላልፏል ልባል እችላለሁ፡፡ ይሁን እንጂ ልዑል ጌታዬ እንደሚያውቁት ፈረንጆች ለትምህርት የዕድሜ ገደብ የለውም ብለው ያምናሉ፡፡ እኔም ዕድሉ ቢደርሰኝ፤ ዕድሜዬ ዕንቅፋት አይሆንብኝም ብዬ አስባለሁ፡፡

አልጋወራሽ፤ ከአነጋገርህ ብልህነትህን መመዘን ይቻላል፡፡ ሆኖም አንድ ነገር ማወቅ ያለብህ ፈረንጆች ለመማር የዕድሜ ገደብ የለውም ሲሉ፤ አንድ ሰው ራሱን ለማሻሻል በየጊዜው አንዳንድ ነገር እየተማረና እያወቀ መኖር ይችላል ማለታቸው ነው እንጂ፤ ተማሪ ቤት ገብቶ መደበኛውን የመጀመሪያውንና የሁለተኛውን ደረጃ ለመማር ከዚያም ዩኒቨርሲቲ ለመቀጠል፤ የዕድሜ ገደብ የለውም ለማለት አይደለም፡፡ እኛም አውሮፓን በጐበኘን ጊዜ፤ ይህን ሁኔታ ደህና አድርገን አጥንተን ተረድተነዋል፡፡

መኰንን ሀ.ወ፤ (ጣልቃ ገብተው) ልዑል ጌታዬ ቢፈቅዱልኝ አቶ ወልደጊዮርጊስ የትምህርት ነገር ያነሣው ያን ጊዜ በዳግማዊ ምኒልክ ተማሪ ቤት የመጀመሪያውን ደረጃ ከፈጸመ በኋላ የነበረውን ምኞት

ለመግለጽ ብሎ ነው እንጂ፤ ዛሬ ወደ ውጭ አገር እንዲልኩት ለማመልከት አይደለም።

አልጋወራሽ፤ ወደ አቶ መኰንን ዘወር ብለው፤ " ... አንተ የእሱን ሐሳብ ከመተርጐም፤ እሱ ምን እንደሚፈለግ ቢናገር አይሻልም? ... "

ወልደጊዮርጊስ፤ (ወጣቱ ወ.ጊ አቶ መኰንን የተናገሩት፤ መስመሩን ለቅቆ አልጋወራሹን እንዳስቆጣ ገባቸው) ... ልዑል ጌታዬ የተናገሩት ትክክል ነው። ወደ ውጭ አገር ቢልኩኝ የሞያ ትምህርት ካልሆነ በስተቀር መደበኛ ተማሪ ቤት ገብቶ ለመማር የዕድሜዬ ጉዳይ አስቸጋሪ እንደሚሆን እኔም ይሰማኛል። አሁን የእኔ ጉዳይ ላለፈው ሳይሆን ከዛሬ ጀምሮ ለወደፊቱ የሚሆነው ነው። ከዚህ ቀደም ለክቡር አቶ መኰንን እንዳመለከትኳቸው፤ እስከዛሬ ተጣጥሬ በተማርኩት ፈረንሣይ፤ በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ተቀጥሬ ብሠራ፤ ልዑልነትዎ ለሚደክሙላት አገራችን ፍሬያማ አገልግሎት ለማበርከት እችላለሁ ብዬ ቃል እገባለሁ።

አልጋወራሽ፤ ይህን ሐሳብ ካንተ ቀደም ብሎ መኰንን አመልክቶናል። በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ፍሬያማ አገልግሎት ለማበርከት ቃል እገባለሁ ስትል፤ ነገሩን በቀላሉ አናየውም። ውሳኔያችንን በቅርቡ እናስታውቅሃለን።

ወልደጊዮርጊስ እጅ ነሥተው ከወጡ በኋላ፤ አልጋወራሽ ከመኰንን ሀብተወልድ ጋር ይወያያሉ።

አልጋወራሽ፤ ይኸ ልጅ ብልህና ጠንካራ መንፈስ ያለው መስሎ ታይቶኛል።

መኰንን ሀ.ወ፤ እኔ አብሬው ሰንብቻለሁ። በጣም ብልህና ንቁ ነው። ይኸ በውጭ ጉዳይ ሥራ ቢመደብ፤ ከውጭ አገር ሰዎች ጋር ላለው የጉዳይ አፈጻጸም በጣም የሚረዳ ነው የሚል ግምት አድሮብኛል። በአንድ ምላስ ሁለት ሐሳብ ወርውሮ በአንዱ ቢሸነፍ በሌላው የሚረታ ነው። ይህን የመሰለውም ችሎታ የውጭ አገር ሰዎችን ተንኮል ለመቋቋም የሚያስችል ነው።

አልጋወራሽ፤ ማለፊያ ነው። ቢሆንም አሁን በቀጥታ ወደ ውጭ ጉዳይ እንዲዛወር ከማድረጋችን በፊት፤ አንድ ሐሳብ መጥቶልኛል። ደጃች ብሩ ወልደገብርኤል* ታሞ ሐኪሞቹ በሽታውን አላገኙለትም። ስለዚህ ፈረንሣይ አገር ሄዶ ምርመራ እንዲያደርግ ከንግሥት ጋር ተነጋግረን ተወስኗል። ለዚህ አብሮት ሄዶ በማስተርጐምና በመድኃኒት አወሳሰድ የሚረዳው ሰው ለማግኘት በማፈላለግ ላይ ነን። አሁን ሳየው፤ ይኸ ልጅ ቢሆን አይሻልም?

---

* በዚያን ጊዜ የወለጋ ጠቅላይ ገዥ፤ የራስ ተፈሪ አብሮ አደግ

መኰንን ሀ.ወ፤ ልዑል ጌታዬ በውነት ፈጣሪ ያመለከተዎ ቢሆን ነው። በጣም ጥሩ ምርጫ ነው። ለዚህም ጠቃሚነቱን በሁለት መንገድ ማየት ይቻላል። የመጀመሪያው ለደጃዝማች ብሩ ጉዳይ ፈረንሣዊኛ አቀላጥፎ የሚናገር፤ ከሐኪሞች ጋር የመሥራት ልምድ ያለው ከዚህ ሰው የተሻለ ማግኘት የሚያዳግት ይመስለኛል። ሁለተኛው ዋና ነገር ነው የምለው፤ ይኸ ልጅ ደጃች ብሩን ለማገልገል በፈረንሣይም አገር በመንገዳቸውም ላይ አብሮአቸው ብዙ ወራት ስለሚቆይ፤ ጠባዩንና ጠቅላላ ታማኝነቱን ለመፈተን ይረዳል። ውጤቱ ማለፊያ ከሆነ፤ ልዑል ጌታዬ ያለአንዳች ማመንታት ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ሲሆን የዋና ጸሐፊነቱን ቦታ፤ ካልተቻለ ደግሞ ቢያንስ የክፍል ኃላፊነትን ቦታ ሊያዙለት ይችላሉ።

አልጋወራሽ፤ ማለፊያ ነው። አሁን ደጃች ብሩን ተከትሎ ፈረንሣይ አገር እንዲሄድ ይዘጋጅ። ሲመለስ፤ ብሩ የሚሰጠንን አስተያየት አዳምጠን ሕሩይም* እንዲያጠናው አድርገን እንወስናለን።

## አቶ ወልደጊዮርጊስ የደጃዝማች ብሩ አስተርጓሚና አስታማሚ ሆነው ወደ አውሮፓ ሄዱ።

የፈረስ ስማቸው "አባ ይሥራው" የተባለውና በዚያን ጊዜ የወለጋ ጠቅላይ ገዥ የነበሩት ደጃዝማች ብሩ ወልደገብርኤል፤ በ1882 ዓ.ም አዲስ አበባ ተወልደው ያደጉት አፄ ምኒልክ ዘንድ ነው። በቤተመንግሥቱ አካባቢ በሹክሹክታ በሚሠራጨው ወሬ፤ ብሩ ወልደገብርኤል ከአፄ ምኒልክ የተወለዱ ናቸው እየተባለ ነበር። ይኸውም ንጉሠ ነገሥቱ በቤተመንግሥታቸው እንደ ልጅ አድርገው ስለአሳደጓቸውና፤ እሳቸውም አንድን ነገር ለማሳመን "እባባ ይሙት" እያሉ ስለሚምሉ፤ የአባ ዳኘው ምኒልክ የምሥጢር ልጅ ናቸው እየተባለ ለሚወራው ወሬ እንደ ማስረጃ ሆኖ ይቀርብ ነበር። ነገር ግን ብሩ ወልደገብርኤል በዚህ ዓለም በኖሩበት በአምሳ አምስት (55) ዓመት የሕይወት ዘመናቸውና ከዚያም በኋላ የምኒልክ ልጅ መሆናቸውን የሚያረጋግጥ በይፋ የታወቀ ነገር አልነበረም።

ራስ ተፈሪና ደጃዝማች ብሩ የሚተዋወቁት በልጅነታቸው ዘመን በአፄ ምኒልክ ቤተመንግሥት ሲሆን፤ ሁለቱም በጃንሆይና እቴጌ እልፍኝ የሚሰጣቸው የፕሮቶኮል መሰብ፤ ከልጅ ኢያሱ ጋር ነበር። አባ ይሥራው ብሩ በተፈጥሮአቸው ደፋርና ልበ ሙሉ መሆናቸው በሰፊው ይነገርላቸዋል። ምናልባትም ከዚሁ ጠባያቸው የተነሣ ሊሆን ይችላል ከሌሎቹ አብሮ አደጐች ከሆኑት መኳንንቶች የተለየ ራስ ተፈሪን "አንተ" እያሉ በመጥራት የዘለቁት ብሩ ወልደገብርኤል ብቻ ናቸው።

ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ የወለጋው ጠቅላይ ገዥ አስተርጓሚና አስታማሚ ሆነው ወደ ፈረንሣይ አገር ጉዞአቸውን ከመጀመራቸው በፊት፤ ደጃዝማች ብሩ ምን ዓይነት ሰው እንደሆኑ፤ ምን ይወዳሉ? ምን ይጠላሉ? ምን

---

* ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ የውጭ ጉዳይ ኃላፊ

ያስቆጣቸዋል? ምንስ ያስደስታቸዋል? በጠቅላላውስ ሰላማዊ ናቸው? ወይስ ግልፍተኛ? እነዚህን የመሳሰሉትን ጠባዮች ለማወቅ፤ ከአባ ይሥራው ዋና ዋና አሽከሮች ጋር በመወያይት ሲያጠኑ ሰንብተው ነበር። ይህን ጥናት በማድረጋቸው፤ ደጃዝማች ብሩ በጉዞአቸው ላይ ስለሚጉበኟቸው አገሮችና ፓሪስም ከደረሱ በኋላ ከሐኪሞች ጋር ስለሚነጋገሩበት ጉዳይ በቅድሚያ አንዳንድ ዋና ዋና ነገሮችን ለማዘጋጀት ረድቷቸዋል። በመሠረቱ፤ ደጃዝማች ብሩን ወደ ፈረንሣይ አገር ሄደው እንዲታከሙ የመከሩት በምኒልክ ሆስፒታል ያሉት ሐኪሞች በመሆናቸው፤ ወልደጊዮርጊስ የበሽተኛውን ፋይል ደህና አድርገው ያውቁ ነበር። ሕመምተኛው ፓሪስ ከደረሱ በኋላ "ሆቴል ዲየ" (Hotel Dieu) በተባለው ሆስፒታል ገብተው በሚታከሙበት ጊዜ፤ ወልደጊዮርጊስ ቀንና ሌሊት ከአጠገባቸው ሳይለዩ የሚደረግላቸውን ሕክምና እየተከታተሉ በማስረዳትና በማስፈጸም፤ የሰጡትን አገልግሎት ብሩ ወልደገብርኤል ጥልቅ በሆነ መንፈስ ተመልክተውታል።

## "ግሩም የሆነ ችሎታ ያለው ሰው ነው"
### የደጃች ብሩ አስተያየት

ብሩ ወልደገብርኤል የተፈሪ መኰንን አብሮ አደግ፤ በፈረንሣይ አገር ጥሩ ሕክምና አግኝተው እግረ መንገዳቸውንም ግሪክን፣ ግብፅንና ኢየሩሳሌምን ጉብኝተው አዲስ አበባ የተመለሱት፤ በተሟላ የደስታ ስሜት ነበር። ልዑል ራስ ተፈሪ መኰንን የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴና አልጋወራሽ ባቡር ጣቢያ ተገኝተው እንኳን ደህና መጣህ ሲሏቸው፤ አባ ይሥራው ብሩ ከሰላምታቸው ቀጥሎ ወዲያውኑ ስለአስተርጓሚያቸው የሰጡት አስተያየት፤ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ግሩም የሆነ ችሎታ ያለው ሰው ነው በሚል ቃል ነበር። ደጃች ብሩ ወልደጊዮርጊስን ያደነቁት፤ በሦስት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ እንደነበረ በሰፊው ተወርቷል። ይኸውም፤

አንደኛ፤ የጤናቸውን ጉዳይ አዲስ አበባ ያሉት ሐኪሞች ያቀረቡትን ሐሳብና፤ ደጃች ብሩ የሚሰማቸውን ሕመም፤ ለፈረንሣዮቹ ሐኪሞች ደህና አድርገው በማስረዳታቸው፤ በሽታቸው ምን እንደሆነ ሊታወቅ በመቻሉ፤

ሁለተኛ፤ ሆስፒታል በቆዩበት ጊዜ፤ ሐኪሞቹ በየዕለቱ የሚያዙላቸውን መድኃኒቶች፤ ሕመምተኛው ሰዓቱን እየጠበቁ በትክክል እንዲወስዱ በማድረጋቸው፤

ሦስተኛ፤ ደጃች ብሩ ከሕመማቸው ከዳኑ በኋላ፤ በልዩ ልዩ ቦታዎች እየተዘዋወሩ ጉብኝት በሚያደርጉበት ጊዜ፤ ለየአገሩ ሹማምንቶች "እኚህ ሰው" ከአልጋወራሽ ተፈሪ ቀጥሎ በመላ ኢትዮጵያ ምን ያህል የተከበሩ ታላቅ ባለሥልጣን መሆናቸውን በማስረዳት፤ አባ ይሥራው የተለየ አቀባበልና መስተንግዶ እንዲያገኙ በማስደረጋቸው ነው ይባላል።

በዚያም ሆነ በዚህ፤ ብሩ ወልደገብርኤል ከአውሮፓ ሕክምናቸው ሲመለሱ የሰጡት ከፍተኛ አስተያየት፤ በአቶ መኰንን ሀብተወልድ የተቀየሰውን የወልደጊዮርጊስን ዕድል አቃንቶ፤ በ1920 ዓ.ም ከሆስፒታል አስተርጓሚነት ወደ ውጭ ጉዳይ ዲፕሎማትነት ለማሻገር አብቅቷል።

በዚያን ዘመን ሚኒስትር ሳይባሉ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርን በሙሉ ኃላፊነት የሚመሩት ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ፣ ለአቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ያዘጋጁላቸው የሥራ መደብ፣ ለጣልያንና ለጀርመን ሌጋሲዮኖች ጉዳይ ኃላፊነትን እንጂ፣ ቀደም ሲል መኰንን ሀብተወልድ ለአልጋወራሹ እንደሰነዘሩት ለሚኒስቴሩ ዋና ጸሐፊነት ሊሆን አልቻለም። በዚህ ጉዳይ ኅሩይ ወልደሥላሴ የሰጡት አስተያየት፣ አንድ ሰው ከተለየ የሥራ ባሕርይ ተነሥቶ ወደ መንግሥት ከፍተኛ ኃላፊነት ማምራት የሚችለው፣ በየደረጃው ያለውን ሥራ በልምድ እያበሰለ ሲሄድ ነው እንጂ፣ በአንድ ጊዜ አናት ላይ ወጥቶ የሥልጣን ወንበር ሲጨበጥ አይደለም። ይህን የመሰለውም ፈጣን እርምጃ፣ ለአስተዳደሩም ሆነ ለሰውየው ጥቅም አይሰጥም የሚል ነበር። በጨዋነታቸውና ሚዛን ባለው አስተያየታቸው የታወቁት ኅሩይ ወልደሥላሴ ያቀረቡትን ሐሳብ አልጋወራሽ ተፈሪ በማጽደቃቸው፣ አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከመስከረም 1920 ዓ.ም ጀምሮ በተወለዱ በሐያ ሰባተኛው ዓመታቸው ከፍተኛ የመንግሥት ሹም ሆኑ።

ወልደጊዮርጊስ በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር አዲሱ ሥራቸውን እንደጀመሩ፣ ከተመደቡባቸው ከጣሊያንና ከጀርመን ሌጋሲዮኖች ጋር የዘረጉት መልካም ግንኙነትና የፈጠሩት መግባባት፣ ለሚቀርቡላቸውም ጥያቄዎች መልሶቹን ሳያዘገዩ በመስጠት፣ ያሳዩት ትጋትና ቅልጥፍና ከሌሎቹ በእኳያቸው ከሚገኙት የሥራ ጓደኞቻቸው ሁሉ የላቀ ችሎታ ያላቸው መሆናቸውን አሳዩ። ከዚህም የተነሣ አንዳንዶቹ የሥራ ጓደኞቻቸው፣ ለካስ የደጃዝማች ብሩ አስተርጓሚ ሆኖ ፈረንሣይ አገር ለጥቂት ወራት ከርሞ መመለስ፣ ዐዋቂ ያስደርግ ኖርዋል ወይ? የሚል የቅናት ወሬ መንዛት ጀምረው ነበር። ሆኖም እነዚህ ሰዎች፣ የወልደጊዮርጊስን ብልህነትና ችሎታ መቋቋም የማይችሉ መሆናቸውን ስለተረዱት፣ ይህንን አለአግባብ የሚሰነዝሩትን ትችት በቶሎ ለማቆም ተገድደዋል። ወልደጊዮርጊስ የሐኪሞች አስተርጓሚ ሆነው በሠሩባቸው ዓመታቶች፣ ከሌሎቹ የውጭ ጉዳይ ሠራተኞች ይልቅ ፈረንሣዊኛቸውን በይበልጥ ለማስፋፋት እንደረዳቸው ለማንም የተሠወረ አይደለም። ቀጥሎም ደጃች ብሩን በማስታመም ፓሪስ በቆዩበት ጊዜ፣ አንዳንድ ለውጭ ጉዳይ ሥራ የሚጠቅሙ ጥናቶች አድርገው ከጓደኞቻቸው የተሻለ የአሠራር ዘዴ በማሳየታቸው፣ የሚደነቁበት እንጂ፣ "ድንገተኛ ዐዋቂ" እየተባሉ የሚተቹበት አልነበረም።

እዚህ ላይ አንድ ከጥንት ጀምሮ የኢትዮጵያ ወዳጅ በመሆኑ የሚኮራ ዘሩ የሶሪያ ተወላጅ፣ ዜግነቱ ፈረንሣይ የሆነ፣ ዠን ኡዋኑ (Jean Ouannou) የሚባል ሰው፣ እ.ኤ.አ በ1956 ዓ.ም በፓሪስ ተማሪ በነበርኩበት ጊዜ ያጫወተኝን ልጠቅሰው እወዳለሁ። " ... ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ለደጃዝማች ብሩ ልዩ ረዳት ሆኖ ፓሪስ በቆየበት ጊዜ፣ እኔ የኢትዮጵያ አፍቃሪ መሆኔን ሰምቶ ከተዋወቀኝ በኋላ፣ በጣም ያስቸግረኝ የነበረው፣

1ኛ/ የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ያለው የሥራ ድርጅትና የዲፕሎማሲ አመራር እንዴት እንደሆነ ለማጥናት ስለሚፈልግ የሚረዳው ሰው እንዳገኝለት፣

2ኛ/ የሠለጠነው የአውሮፓው ዓለም የሚከተለውን የዲፕሎማሲ ሥራ የሚያስረዳ መጽሐፍ ፈልጌ እንድገዛለት ነበር።

እነዚህን ሁለት ነገሮች እንድፈጽምለት እየደጋገመ ስለአስጨነቀኝ፣ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ከ ኬ ዶርሰይ (Quai D'orsay) ጋር ተነጋግሬ፣ ወልደጊዮርጊስ ለአሥር ቀናት በየዲፓርትመንቱ እየተዘዋወረ ጥናት እንዲያደረግ አስፈቀድኩለት። ነገር ግን ይሂቸው የመጣው ትልቁ ጌታ ብሩ ወልደገብርኤል፣ ዐሥር ቀን ሙሉ ከአጠገቤ መለየት ስለሌለብህ፣ የአምስት ቀናት ጥናት ብታደርግ ይበቃሀል ብለው አስቸገሩት። በመጨረሻው የእኔም አማላጅነት ተጨምሮበት፣ ለዐሥር ቀናት ያገኘውን ዕድል እንዲጠቀምበት ራስ ብሩ ስለፈቀዱለት፣ ወልደጊዮርጊስ ከመጠን በላይ ተደስቶ ነበር። ከዚህም ቀጥሎ የጠየቀኝን የትምህርት መጽሐፍ ለማግኘት ብዙ ከተቸገርኩ በኋላ፣ በፖለቲካ ሣይንስ ትምህርት ቤት "የዲፕሎማሲ ሀሁ" የተባለች ከመቶ ገጽ የማትበልጥ አንዲት ሥነ ጽሑፍ አግኝቼ ገዛሁለት። እኔ ይህን ሁሉ እርዳታ ሳደርግለት፣ ኢትዮጵያንና ልጆቿን በማፍቀር እንጂ፣ ወልደጊዮርጊስ አንድ ቀን ትልቅ ባለሥልጣን ይሆናል ብዬ በማለም አልነበረም። ነገር ግን ጊዜው ተለዋውጦ ከዐሥራ አምስት ዓመታት በኋላ፣ ያ የዲፕሎማሲን ሀሁ ለማጥናት ይጥር የነበረ ወጣት፣ ከኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት ጠቅላይ ሚኒስትር የበለጠ ባለሙሉ ሥልጣን ሆኖ ሳገኘው እጅግ ተገረምኩ። እሱም ያችን ከዐሥራ አምስት ዓመታት በፊት ያደረግኩለትን መጠነኛ እርዳታ በማሰብ፣ በፓሪስ የኢትዮጵያ ኤምባሲ የንግድ አማካሪ ሆኜ በምሠራበት ጊዜ በአንዳንድ ጉዳዮች ረድቶኛል ... "

እኔ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ከአምሳ ዓመታት በፊት የማስታውሰውን ይህን የአንድ የውጭ አገር ሰው አስተያየት ዛሬ ስመለከተው፣ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከልጅነታቸው ጀምሮ ለመማርና ብዙ ለማወቅ ያላቸው ፍላጐት፣ ምን ያህል ከፍተኛ እንደነበረ የሚያሳይ ሆኖ አግኝቼዋለሁ። ፓሪስ የመጡበትን ጉዳይ ፈጽመው ወደ አገራቸው ሲመለሱ፣ በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የመሥራት ዕድል አለኝ በሚል ተስፋ፣ የዲፕሎማሲ ሞያና የተግባር አፈጻጸም እንዴት እንደሆነ በአጭር ጊዜ ውስጥ ለማጥናት ብርቱ ጥረት ማድረጋቸው፣ እርቀ አሳቢነታቸውን ብቻ ሳይሆን፣ ለዕድገት ያላቸውንም ቀራጥነት የሚያመለክት መሆኑን መገንዘብ ይቻላል።

ከዚህ ሁሉ በላይ ደግሞ፣ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ በታሪካቸው ለመጀመሪያ ጊዜ በመንግሥት መሥሪያ ቤት የክፍል ሹም ሆነው እንዲሠሩ ዕድሉ ከተሰጣቸው በኋላ፣ በሰባት ዓመታት ጊዜ ውስጥ፣ ከአልጋወራሹ ጋር የዘረጉት መልካም ግንኙነትና ያደረጉት የሥልጣን ዕድገት፣ ከዚህ ቀደም ማንም ያልደረሰበት ነው ተብሎ በሰፊው ተደንቋል። ይኸውም፣

1ኛ/ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የክፍል ሹም፣
2ኛ/ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ፣
3ኛ/ የንጉሠ ነገሥቱ ልዩ ጸሐፊ፣
4ኛ/ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር

ለመሆን የቻሉት፣ በሰውየው ብልህነት? ወይስ በእጋር ብዛት? በየትኛው እንደሆነ መልሱን ለማግኘት የታሪኩን ሂደት በጥልቀት ማየት ያስፈልጋል።

# ወልደጊዮርጊስ ከአልጋወራሽ ጋር

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት አልጋወራሽና ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴ፣ (ጊሳ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ) በወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ላይ መልካም አስተያየታቸውን መስጠት የጀመሩት፣ ወጣቱ ዲፕሎማት በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የጣልያንና የጀርመን ሌጋሲዮኖች ጉዳይ ኃላፊ ሆነው ከሚሠሩበት ጊዜ ጀምሮ ነው።

አልጋወራሽ ተፈሪ ከሌሎቹ የአውሮፓ አገሮች ሁሉ የጣልያኑን የሙሶሊኒን መንግሥት ጉዳይ በየዕለቱ አጥብቀው ይከታተሉ ስለነበረ፣ የዚህ ክፍል ኃላፊ የሆኑትን ወልደጊዮርጊስን በቅርብ ለማወቅ፣ እንዲሁም ትጋታቸውንና የሥራ ጥራታቸውን ለመገመት አስችሏቸዋል። ብልሁ ወልደጊዮርጊስም ይህ ዕድል ስለገጠማቸው፣ አለቃቸውን የውጭ ጉዳይ ዋናውን ኃላፊ ብላቴን ጌታ ኅሩይን እያለፉ፣ በቀጥታ ከአልጋወራሽ ንጉሥ ተፈሪ ጋር የሥራ ግንኙነታቸውን እያስፋፉ ሄዱ። አልጋወራሽ ንጉሥ ተፈሪም የወጣቱ ዲፕሎማት ሥራ ከዕለት ወደ ዕለት እየጣማቸው ስለሄደ፣ የውጭ ጉዳዩ ዋና ኃላፊ ቅር ቢላቸውም ባይላቸውም፣ ወልደጊዮርጊስን እየጠሩ ማነጋገርና ቀጥታ መምሪያ መስጠታቸውን ቀጠሉበት። በዚህ አኳኋን ወልደጊዮርጊስ ከአልጋወራሽ ጋር ያላቸውን ልዩ ግንኙነት ቀስ በቀስ ሰው ሁሉ እያወቀው ስለመጣ፣ በዚያው መጠን ወሬውም እየተጨማመረበት ተነዛ።

በዚያን ዘመን የአልጋወራሽ ተፈሪ ዋና የእልፍኝ አሽከር የነበሩት ፊታውራሪ ሣህሌ ድልነሣሁ (ጊላ ደጃዝማች ሴናተር) አንድ ጊዜ ይኸን የቀድሞውን ታሪክ እንሥተው ለክቡር አቶ ጌታሁን ተሰማ (የቀ.ኃ.ሥ ካቢኔ ሚኒስትር) ሲያጫውቷቸው እንደሰማሁት፣ ንጉሥ ተፈሪ አቶ ወልደጊዮርጊስን ለከፍተኛ ደረጃ እንደሚያዘጋጇቸው ብዙ ሰዎች ያተኩሩት፣ የንግሣቸውን በዓል ፕሮግራም በሚያሰናዱበት ጊዜ ነበር።

አልጋወራሹ፣ ዋና ዋናዎቹን መሳፍንትና ሚኒስትሮቹን ሰብስበው ስለ ጠቅላላው የንግሥ በዓል ዝግጅት በተነጋገሩበት ጊዜ፣ ከውጭ አገር ተጋብዘው የሚመጡትን የየነገሥታቱንና የየመንግሥታቱን እንደራሴዎች፣ ባቡር ጣቢያ* ተገኝተው የሚቀበሏቸው፣ ከመሳፍንት ልዑል ራስ ካሣ ኃይሉ፣ ከታላላቅ ሚኒስትሮች ክቡር ራስ ብሩ ወልደገብርኤል የጦር ሚኒስትር እንዲሆኑና፣ ከእነሱም ጋር የቤተመንግሥቱ ሊጋባና የአዲስ አበባ ከተማ ከንቲባ እንዲገኙ ተወስኖ ነበር። ይህ ውሳኔ ተደርጐ በይፋ ከመገለጹ በፊት፣ ፈጣኑ ወልደጊዮርጊስ ለአልጋወራሽ ንጉሥ ተፈሪ አንድ ልዩ ማስታወሻ ያቀርቡላቸዋል። ፊታውራሪ ሣህሌ ትዝ እንደሚላቸው፣ ከወልደጊዮርጊስ የቀረበው ሐሳብ የሚከተለው ነበር።

ለበዓሉ ተካፋይ ለመሆን ከሚመጡት የውጭ መንግሥታት መልዕክተኞች መካከል፣ ለነፃነታችንና ለኤኮኖሚ ጥቅማችን ሲባል፣ የአራቱን ታላላቅ አገሮች የእንግሊዝንና የአሜሪካንን፣ የፈረንሣይንና የጣልያንን እንደራሴዎች ባቡር ጣቢያ ሄደው የሚቀበሏቸው ራሳቸው አልጋወራሽ ቢሆኑ ይሻላል። ከእነዚህ ከአራቱ በስተቀር ከሌሎች አገሮች የሚመጡትን መላክተኞች እንደየደረጃቸው ሚኒስትሮች

---

* በዚያን ዘመን በኢትዮጵያ የመጓጓዣ አውሮፕላን አልነበረም።



አልጋወራሽ ንጉሥ ተፈሪ መኰንን ለንግሣቸው በዓል አዲስ አበባ የሚመጡትን የመንግሥታት እንደራሴዎች ባቡር ጣቢያ ሲቀበሉ፤ አጠገባቸው በአገር ልብስ የሚታዩት ወጣቱ ዲፕሎማት የጀርመንና የጣልያን ጉዳይ ኃላፊ፤ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ናቸው፤

እየታዘዙ ሊቀበሏቸው ይችላሉ። ከበዓሉ ፍጻሜ በኋላ ግን፣ የመሸኘቱ ጉዳይ የተለየ መሆን አለበት። የአራቱን ታላላቅ አገሮች እንደራሴዎች፣ ንጉሠ ነገሥቱ የሚያሰናብቷቸው በቤተመንግሥታቸው ሲሆን፣ ባቡር ጣቢያ የሚሸኟቸው አዲሱ የኢትዮጵያ ን.ነ.መ አልጋወራሽ ልዑል መርዕድ አዝማች አስፋወሰን ቢሆኑ የተገባ ይመስለኛል የሚል ነው።

አልጋወራሹ ይህ ማስታወሻ ሲደርሳቸው፣ ምን ያህል እንደተደሰቱና በወልደጊዮርጊስም ላይ ከፍተኛ አድናቆት እንደአደረባቸው በግልጽ ይታይባቸው ነበር። ወዲያውም ብላቴን ጌታ ኅሩይን ጠርተው፣ ስም ሳይገልጹ አንድ ሰው ይህን የመሰለ ሐሳብ አቅርቦልኝ ነበር። አንተስ ምን ይመስልሃል? ብለው ጠየቋቸው። ኅሩይ ወልደሥላሴ ይህ ሐሳብ በየት ቀዳዳ ሾልኮ ብቅ እንዳለ ቢያውቁም፣ ዝርዝሩ ውስጥ ሳይገቡ በአጭሩ፣ ለዚህ ክብረ በዓል ጉዳይ ተካፋይ ለሚሆኑት እንግዶች፣ የታላላቅና የታናናሽ አገሮች እያሉ በአቀባበል ፕሮቶኮል መለያየት የተገባ አይሆንም። የመልዕክተኞቹ ደረጃ ዝቅ ያለ ካልሆነ በስተቀር፣ የሁሉንም መንግሥታት እንደራሴዎች በእኩል ደረጃ አልጋወራሽ ባቡር ጣቢያ እየተገኙ ቢቀበሏቸው ይሻላል አሉ። በመጨረሻው በዚህ በብላታ ኅሩይ ሐሳብ ራስ ካሣም ስለተስማሙ፣ ከውጭ አገር የሚመጡት እንግዶች ደረጃቸው ዝቅተኛ ካልሆነ በስተቀር፣ ሌሎቹን በትልቅ ደረጃ የሚመጡትን በሙሉ ራሳቸው አልጋወራሹ ባቡር ጣቢያ ተገኝተው እንዲቀበሉ ተወሰነ። ይህ ሁሉ ከሆነ በኋላ፣ በአልጋወራሽ ተፈሪ አስተያየት ለዚህ ለእንግዶች አቀባበል ጉዳይ፣ ብላቴን ጌታ ኅሩይ በሰጡት ማሻሻያ መሠረት ፕሮግራሙ ቢፈጸምም፣ ከሰው በፊት በቅድሚያ አጥንቶ ሐሳቡን ያቀረበልን ወልደጊዮርጊስ ነው በማለት፣ አድናቆታቸውንና ምሥጋናቸውን ከመግለጽ ችላ አላሉም።

እንግዲህ እንደሚታየው፣ ወልደጊዮርጊስ ከአልጋወራሹ ጋር የጀመሩት ባለሟልነት ከጊዜ ወደ ጊዜ እየዳበረ በመሄዱ፣ በዙሪያቸው ብዙ ተቃዋሚዎች መነሣታቸውና ለእድገታቸው እንቅፋት ለመሆን መፍጨርጨራቸው አልቀረም ነበር። ነገር ግን ተፈሪ መኰንን በአልጋወራሽነት ዘመናቸውና ቀጥሎም ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት ተብለው ዘውድ ከጫኑ በኋላ፣ ወልደጊዮርጊስን ማቅረባቸውንና በሥራቸውም መደሰታቸውን ስለቀጠሉ፣ ተቃዋሚዎቻቸው ዒላማቸውን ለመምታት አልተሳካላቸውም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የንግሥ በዓላቸውን ባከበሩ በስድስተኛው ወር፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነታቸውን በኦፊሲየል ያጸደቁላቸው ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ፣ የወልደጊዮርጊስን ብልህነትና ጠንካራ ሠራተኛነታቸውን ቢያምኑበትም፣ በአንድ ሰው ላይ አለመጠን የተፋጠነ ሹመትና ዕድገት መስጠት በአጭር እንዳይቀጭ እርጋታ ቢጨመርበት ይሻላል፣ የሚለውን አስተያየታቸውን መለወጥ አልፈለጉም። ወልደጊዮርጊስ ደግሞ በተለይ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን የንግሥ በዓል፣ በተመደቡበት ቦታ ፍሬያማ አገልግሎት ካበረከቱ በኋላ፣ ከጣልያንና ጀርመን ሌጋሲዮን ኃላፊነት ወደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነት በምን ምርኩዝ መሻገር እንደሚችሉ አልታይ ብሏቸው ተቸግረው ነበር።

አንድ ቀን ንጉሠ ነገሥቱ፣ (በሐምሌ 1924 ዓ.ም ነው ይባላል) የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊ የሆኑትን አቶ ገብረወልድ እንግዳወርቅን (ኋላ ም/ጸሐፊ ትእዛዝ) ጠርተው፣ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ለብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ አንድ ማስታወሻ እንዲላክ ያዛሉ። ቃሉም፣ "አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ

የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነቱ ሊሰጠው ይገባል ብለን እናምናለን። ያንተን ሐሳብ በቶሎ እንድታቀርብልን ይሁን" የሚል ነበር። ብላቴን ጌታ ወዲያውኑ ባቀረቡት ማስታወሻ፤ " ... ባሪያዎ ጃንሆይ ያመኑበትን በትክክል ለመፈጸም ከመዘጋጀቴ በስተቀር፤ የማክለው የለኝም" አሉ።* የኅሩይ ወልደሥላሴ አስተያየት፤ በሌላ አነጋገር እርስዎ ያመኑበትን ጉዳይ ከመፈጸም በስተቀር፤ የእኔ አስተያየት ምን ቦታ ይኖረዋል? የሚል ነው ተብሎ ሳይተረጐም አልቀረም። ያም ሆነ ይህ፤ የአባ ጠቅል ፍላጐት ከተግባር ላይ ውሎ፤ አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከውጭ ጉዳይ የክፍል ኃላፊነት የሚኒስቴሩን ዋና ጸሐፊነት በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ንጉሠ ነገሥት ዘኢትዮጵያ ለመሾም በቅተዋል።

ፈጣኑ ወልደጊዮርጊስ ሲመኙት የነበረውን የዋና ጸሐፊነቱን ቦታ ከተሾሙ በኋላ፤ ከሚኒስትሩ ከብላቴን ጌታ ኅሩይ ቀጥሎ ለጠቅላላው የውጭ ጉዳይ ሥራ አመራር አስተባባሪው እኔ ነኝ አሉ። በመሠረቱ ቀደም ሲል በነበረው ሥርዓት፤ የሚኒስቴሩን በጀትና የሠራተኞቹን አስተዳደር በበላይነት የሚመራው ዋናው ጸሐፊ ቢሆንም፤ የወልደጊዮርጊስ አያያዝ ድንበር እያለፈ ሥልጣን የሚያስፋፋ ሆኖ ብቅ አለ። ይኸውም፤ በፖለቲካው ጉዳይ ኢትዮጵያ ከውጭ መንግሥታት ጋር ስለአላት ግንኙነት ለየአገሮቹ እየተመደቡ የሚሠሩት ሹማምንቶች ሁሉ፤ ቀድሞ በቀጥታ ለሚኒስትሩ የሚጽፉት ራፖር፤ አሁን በአዲሱ በወልደጊዮርጊስ ፕላን መጀመሪያ ለዋናው ጸሐፊ ቀርቦ አስተያየት ከተሰጠበት በኋላ፤ ለውሳኔ ወደ ሚኒስትሩ ይተላለፋል የሚል ሆነ።

ይህ አሠራር ቀድሞ እንዴት እንደነበረ ወደ ኋላ ተመልሶ ሲታይ፤ ወልደጊዮርጊስ ራሳቸው የጣልያንና የጀርመን ጉዳይ ኃላፊ ሆነው በሠሩበት ጊዜ፤ ከእሳቸው በፊት ለነበረው ዋና ጸሐፊ እንኳንስ ራፖራቸውን ለማቅረብ ይቅርና፤ እንዲያውቁትም ብለው ግልባጩን እንኳ አይልኩለትም ነበር። ከዚያም በላይ፤ ዋናውን አለቃቸውን ብላቴን ጌታ ኅሩይን እያለፉ በቀጥታ ከአልጋወራሽ ተፈሪ ጋር መሥራታቸውና መምሪያም መቀበላቸው ይህን ያህል የተደበቀ ምሥጢር አልነበረም። አሁን ግን እሳቸው ዋና ጸሐፊ ሲሆኑ፤ የየክፍሉ ሹማምንቶች ሁሉ የበላዮቻቸውን ቅደም ተከተል እያከበሩ መሥራት አለባቸው የሚል ሐሳብ አመጡ።

ኅሩይ ወልደሥላሴ ይህን የወልደጊዮርጊስን አዲስ የአሠራር ፕላን ከተመለከቱ በኋላ፤ ሰውየውን ጠርተው " ... በዋና ጸሐፊነትህ የሚኒስቴሩን ሥራ በሙሉ የምትቆጣጠረውና የምትመራው አንተ ብቻ ከሆንክ፤ ለእኔ ለሚኒስትሩ የየትኛውን ክፍል ሥራ መድበህልኛል? ... " ብለው ጠየቋቸው። የኅሩይ ጥያቄ በሌላ አነጋገር፤ የሚኒስቴሩን ልዩ ልዩ የሥራ ዘርፎች የሚመራውና የሚቆጣጠረው ዋናው ጸሐፊ ከሆነ፤ የሚኒስትሩ የዕለት ተግባር ምን ሊሆን ነው? የሚል ነበር። ወልደጊዮርጊስ ግን ጥያቄውን በቅድሚያ አውቀው፤ መልሱንም በቅድሚያ አዘጋጅተው የጠበቁ መስለው ተገኝተዋል። " ... በእኔ አስተያየት፤ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የዋና ጸሐፊነት ሥራ የተፈጠረው፤ እንዲሁ ስምና ወግ ይዞ ለመቀመጥ አይደለም። ከሚኒስትሩ የሚሰጡትን መምሪያዎች ሁሉ የፖለቲካና የአስተዳደር ነክ የሆኑትን እየለየ፤ ጉዳዩ ለሚመለከታቸው ልዩ ልዩ ክፍሎች ማስተላለፍ የመጀመሪያ ተግባሩ ሲሆን፤ ቀጥሎ ደግሞ በተሰጠው መምሪያ መሠረት የተፈጸሙትን ሥራዎች ሰብስቦ እያጣራ፤ ከአስተያየት ጋር ለሚኒስትሩ በማቅረብ

---

* ም/ጸሐፊ ትዕዛዝ ገብረወልድና አባቴ ቀኛ/ረታ፤ ሲጨዋወቱ እንደሰማሁት

ውሳኔ እንዲሰጥባቸው ማድረግ ነው። ይህንንም የመሰለው አሠራር፣ አንድ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ከዝርዝር ሥራዎች ነፃ ሆኖ የዓለምን የፖለቲካ ሁኔታ በየዕለቱ ለመከታተልና ከታላቁ መሪውም ጋር እየተመካከረ፣ የአገሩን ፖሊሲ ለመመሥረት የሚያስፈልገውን ጊዜ ለማግኘት የሚረዳው ነው። ከቡርነትዎ እንደሚያውቀው ይህን አሠራር በሥልጣኔ የገፉትና ወደ ሥልጣኔም ለማምራት የሚጥሩት አገሮች ሁሉ ስለሚጠቀሙበት፣ እስከዛሬ የታየው ውጤት እጅግ ፍሬያማ መሆኑ በሰፊው ይነገራል። እኔም በፓሪስ የፈረንሣይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ለጥቂት ቀናት ያጠናሁትን የአሠራር ዘዴ ለከቡርነትዎ ያቀረብኩት፣ ያለብዎትን ከፍተኛ የፖለቲካ ኃላፊነት በሚገባ ለማካሄድ እንዲያመችዎ፣ በየዕለቱ እየተከማቹ የሚያስቸግሩትን ስንክሣሮች ዋናው ጸሐፊ እንዲመክትልዎ በማሰብ ነው እንጂ፣ እኔ በግሌ የተለየ ጥቅም አገኝበታለሁ ብዬ አይደለም። ያቀረብኩትን አዲስ የአሠራር ዘዴ አብዛኛዎቹ የክፍል ሹማምንቶች የሚቃወሙት፣ ኃላፊነታችንና ተጠሪነታችን ቀጥታ ለሚኒስትሩ መሆኑ ቀርቶ፣ በዋናው ጸሐፊ በኩል እንድንታዘዝ ተደርጐብናል በማለት ነው። የቀረበው ፕላን፣ የየክፍሉ ሹማምንቶች ኃላፊነታቸው ለሚኒስትሩ መሆኑ ተለውጧል አይልም። በዚህ መልክ እየተረጐሙ ተቃውሞአቸውን በያለበት የሚነዙት ሰዎች፣ መሻሻልን የማይፈልጉትና በችሎታቸው የማይተማመኑ ሰነፎቹ ናቸው ... " በማለት ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ማብራሪያቸውን ለሚኒስትሩ በሰፊው አቀረቡ።

ብላቴን ጌታ ኅሩይ፣ ከወልደጊዮርጊስ የቀረበላቸው የአሠራር ፕላን ግቡ ምን መሆኑን ተረድተውታል። ... የሚኒስትሩ የሥራ ሰዓቶች በዝርዝር ጉዳዮች ላይ እንዳይባክኑና፣ ለታላላቆቹ ሥራዎች ማከናወኛ እንዲውሉ ለማድረግ ነው በማለት አሰማምረው የሚናገሩት፣ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋናው የሥራ አስተባባሪ እኔ ነኝ ለማለት መሆኑን ተገንዝበውታል። እንደዚሁም በዚህ በወልደጊዮርጊስ ፕላን ጆርባ፣ የተፈሪ መኰንን ማበረታቻ ሳይኖርበት አይቀርም የሚል ጥርጣሬ አድሮባቸዋል። በዚህ ሁኔታ ፕላኑ ይቆይ፣ ብሎ ማገዱ፣ ከንጉሠ ነገሥቱ የሚመጣው የድጋፍ ትዕዛዝ፣ በግዴታ እንዲፈጸም ያደርገዋል። ይሁን፣ ብሎ መፍቀዱ ደግሞ፣ ብዙዎቹን የውጭ ጉዳይ ሹማምንቶች እጅግ ቅር ያሰኛቸዋል። እንግዲህ ምን ይሻላል? የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ብዙ ካሰቡበት በኋላ፣ ለወልደጊዮርጊስ ፕላን አንድ ዓይነት መውጫ መንገድ በመፈለግ የሚከተለውን መምሪያ ለሁሉም አስተላለፉ። " ... አገራችን በአሁኑ ሰዓት ከውጭ መንግሥታት ጋር ስለአሏት ግንኙነቶች እንድፈጽማቸው ከንጉሠ ነገሥታችን የተሰጡኝ ሥራዎች እጅግ ብዙዎች በመሆናቸው፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስቴርን ዝርዝር የሆኑ የዕለት ሥራዎች እያጠናሁ አፋጣኝ ውሳኔ ለመስጠት ጊዜ አጥሮኛል። በዚህ ምክንያት የሚኒስቴሩ ሥራ እንዳይበደል፣ ለጊዜው እኔን በቅርብ የሚረዳኝ አንድ ሰው መመደብ አስፈላጊ ስለሆነ፣ ዋናው ጸሐፊ በአስተዳደርና በፐርሶኔል ጉዳይ ካለው ኃላፊነት በተጨማሪ፣ የፖለቲካውን ጉዳይ ከሚከታተሉት የክፍል ሹማምንቶች ወደ እኔ የሚላኩትን ራፖሮች እየተቀበለ፣ ከአስተያየት ጋር ለውሳኔ በሚያመች አኳኋን እንዲያቀርብልኝ አድርጌአለሁ። በሕብረት የሚከናወን ሥራ ሁሉ ለአገር እንደሚጠቅም የታወቀ ስለሆነ፣ ሁላችሁም ይህንኑ ተከትላችሁ እንድትሠሩ አደራ እላለሁ ... "

ከዚህ በላይ እንደታየው ከብላቴን ጌታ በተሰጠው መምሪያ፣ ወልደጊዮርጊስ ለፖለቲካው ክፍል ሹማምንቶች ቀጥታ አለቃ ናቸው ተብሎ ባይጠቀሱም፣ የሚኒስትሩ የቅርብ ረዳትና የውሳኔ ሐሳብ አቅራቢ መባላቸው፣ ቀድሞ ከነበራቸው ተጨማሪ ሥልጣን ማግኘታቸውን የሚያመለክት ነው። ፈጣኑ ወልደጊዮርጊስ



ክቡር ብላቴን ጌታ ኅሩይ ወልደሥላሴ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር።

ይህን ካገኙ በኋላ፤ ወሰን እየጣሱ የሥልጣናቸውን ሜዳ ለማስፋፋት ጊዜ አላጠፉም። ከክፍል ሹማምንቶቹ የሚዘጋጁትን ራፖሮች እየተቀበሉ ከአስተያየት ጋር ለሚኒስትሩ ውሳኔ እንዲያቀርቡ በተባለው መምሪያ ብቻ መቆም አልፈለጉም። የልዩ ልዩ አገሮች የፖለቲካ ጉዳይ ኃላፊዎች ራፖራቸውን በምን መልክ እንደሚያዘጋጁና በስንት ጊዜ ውስጥ አጠናቅቀው ማቅረብ እንዳለባቸው፤ ወልደጊዮርጊስ በራሳቸው ሥልጣን መምሪያ መስጠት ጀመሩ። በዚህ አኳኋን በጥቂት ወራቶች ውስጥ የወልደጊዮርጊስ የዋና ጸሐፊነት ሥራ ከምክትል ሚኒስትር የበለጠ ሥልጣን ይዞ ታየ። እነዚያም በመጀመሪያ ዋናው ጸሐፊ ለምን ይገባብናል በማለት የመቃወም ድምፅ ያሰሙት ሹማምንቶች መምሪያውን አሜን ብለው መቀበል ብቻ ሳይሆን፤ ከዚያም አልፈው የወልደጊዮርጊስ አሠራር ለሥራችን ቅልጥፍና ሰጥቶናል የሚል አድናቆት ጨመሩበት። ሹማምንቶቹ ይህን ሲያደርጉ ከልባቸው አምነውበትና ተቀብለውት ሳይሆን፤ ተቃውሞአቸውን መቀጠል ችግራቸውን ከማባባስ በስተቀር፤ ውጤት እንደማይሰጣቸው ስለተረዱት ነው።

## ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ
## የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ጠንካራ ሠራተኛነትና ብልህነት መልካም አስተያየት ያደረባቸው፤ በተለይ የንግሥ በዓላቸውን ለማክበር በሚያዘጋጁበት ጊዜ በ1923 ዓ.ም እንደነበረ ይታወሳል።

በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር የጣልያንና የጀርመን ለጋሲዮኖች ኃላፊ ሆነው በተመደቡበት ቦታ፤ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ያሳዩት ትጋትና የሥራ ጥራት የሚያስደስት ሆኖ በመገኘቱ፤ የንጉሠ ነገሥቱ መልካም ፈቃድ ሆኖ የሚኒስቴሩ ዋና ጸሐፊ ሆነው ለመሾም በቁ። ይህንንም ሥልጣን ከተቀበሉበት እንሥቶ ሁለት ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ለውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ሥራ ማሻሻያ በየጊዜው የሚያቀርቡት ሐሳብና በዚያውም መጠን የራሳቸውን ሥልጣን ለማስፋፋት የሚያደርጉት ጥረት፤ በብዙዎቹ ታላላቅ ሰዎችና የውጭ አገር ዲፕሎማቶች ዘንድ የታወቁ ሰው ሆነዋል። በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ውስጥ ያሉት ሹማምንቶች ሁሉ ፊት ለፊት ሰጥ ለጥ ብለው ቢታዘዟቸውም፤ በጀርባ ሊያጠቋቸውና ሊያጠፏቸው መሞከራቸው አልቀረም ነበር። ሆኖም የሰውየው ጠንካራነትና ንቃት ከሁሉም የበለጠ ስለሆነ፤ የተቃዋሚዎቻቸውን ተንኮል ለመቋቋም ደካማ አልሆኑም።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዚያን ዘመን የሥራ ትጋትና ብልህነት ከሚታይባቸው ወጣቶች አንዱ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ሆነው ስለአገኟቸው፤ የማንንም ሐሳብ ሳይጠይቁ፤ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ዋና ጸሐፊነት አንሥተው ለጥቂት ወራት ልዩ ጸሐፊያቸው በማድረግ የሥራ ጠባያቸውን ካላመዷቸው በኋላ፤ በ1927 ዓ.ም የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ብለው ሾሟቸው።

ይህ ከፍተኛ ሹመት በአዋጅ ከተነገረ በኋላ፤ ንጉሠ ነገሥቱ በተለይ ወልደጊዮርጊስን ጠርተው፤ " ... ያሳደግኩትን አበባ እኔው ቆርጬ መጣሉ ከሁሉ የበለጠ የሚያሳዝነኝ ስለሚሆን፤ ይህ ኃዘን እንዳይደርስብኝ ተጠንቀቅ ... " ብለው እጅግ የከበደ የምክር ቃል ጣሉባቸው። ይህ ቃል ከተነገራቸው ከጥቂት ዓመታት በኋላ ጃንሆይ በስደት በእንግሊዝ አገር በሚኖሩበት ጊዜ፤ ወልደጊዮርጊስ



አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤
የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆነው ተሾሙ። (1927 ዓ.ም)
" ... የማሳድገውን አበባ እኔው ቆርጬ መጣሉ ስለሚያሳዝነኝ፤ ይኸ ኃዘን እንዳይደርስብኝ ተጠንቀቅ ... " (ቀ.ኃ.ሥ በሹመቱ ጊዜ ለተሿሚው የተናገሩት)

በብዕራቸው ደብዳቤ ጽፈው አስታውሰዋቸዋል።* ወልደጊዮርጊስ በደብዳቤያቸው ላይ የጠቀሱት፤ አበባው ተቀርጦ ጃንሆይ አዘኑ፤ ወይም አበባው አብቦ ጃንሆይ ተደሰቱ! ለማለት ሳይሆን፤ በአእምሮአቸው ተቀርጾ የኖረውን ከፍተኛ የምክር ቃል፤ በስደቱ ሕይወት ያልዘነጉት መሆኑን ለመናገር ነው። የዚህ ቃል ታሪክ እዚህ ላይ አይቆምም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያሳደጉትን አበባ ከሐያ ዓመታት በኋላ ራሳቸው ቀጠፉት? ወይስ በሌሎች አስቀጠፉት? ታሪኩን በመከተል ጊዜው ሲደርስ እውነተኛውን መልስ እናገኘዋለን።

እንግዲህ! የቀድሞው የምኒልክ ሆስፒታል አስተርጓሚ፤ በውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር ከተሰጣቸው የክፍል ኃላፊነት ተነሥተው ዋና ጸሐፊ ለመሆን የበቁትና፤ ከዚያም ተውዘግዝገው የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ተብለው የተሾሙት፤ ከ1920 እስከ 1927 ዓ.ም ድረስ ባለው በሰባት ዓመታት ጊዜ ውስጥ መሆኑን ከዚህ በላይ የተገለጸው ታሪካቸው አስረድቷል።

በዚህ ምዕራፍ ውስጥ ምንም እንኳ ያደረጉት የሥራ ዕድገት በየመልኩ እየተዘረዘረ ቢቀርብም፤ በዚህ በአጭር ጊዜ ውስጥ ይህን ሁሉ ደረጃ የወጡት ያለጥርጥር በታላላቆች ድጋፍና የተለየ እርዳታ መሆን አለበት የሚል አስተያየት ሊቀርብ ይችላል። የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ረዥም ጊዜ የወሰደ ምርምር አድርጓል። የብዙዎቹንም ታላላቅ ሰዎች አስተያየት ተከታትሎ አዳምጧል። ከዚህ ሁሉ ጥናት በኋላ፤ ደራሲው ትክክለኛ መስሎ የታየውን አስተያየት የሚያቀረበው እንደሚከተለው ነው።

ወልደጊዮርጊስ ከሆስፒታል አስተርጓሚነት ወደ ውጭ ጉዳይ ሚኒስቴር እንዲዛወሩ፣ መኩንን ሀብተወልድ ከአልጋወራሽ ተፈሪ ጋር በማስተዋወቅ የመጀመሪያው ምክንያት መሆናቸውንና፣ ብሩ ወልደገብርኤል ደግሞ የሰጡት የጋለ የድጋፍ አስተያየት፣ የሰውየውን ዕድል ወደ መልካም መንገድ ለመምራት የረዳ መሆኑን መካድ አይቻልም። ከዚህ በኋላ ግን፣ ወልደጊዮርጊስ በሰባት ዓመታት ጊዜ ውስጥ፤ ከዕድገት ወደ ዕድገት ለመሸጋገር የቻሉት እና ከዚያም የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተርነትን የሚያህል ሥልጣን ለማግኘት የበቁት፤ በራሳቸው ትጋትና በተለይም በችሎታቸው ኃይል መሆኑን ማመን ያስፈልጋል።

ወልደጊዮርጊስ የጽሕፈት ሚኒስቴር ዋና ዲሬክተር ሆነው የተሾሙት በጣልያን ጦርነት ዋዜማ ስለነበረ፤ ንጉሠ ነገሥቱን ተከትለው ማይጨው ከዘመቱ በኋላ ወደ ገኔቭ አብረው ሄደው፤ ከዚያም በአምስቱ ዓመታት የመከራ ዘመን የስደተኛው ንጉሠ ነገሥት ቀኝ እጅ ሆነው እስከ መጨረሻው ሳይለዩ የቆዩ ናቸው።

ነፃነት ከተመለሰ በኋላ ከ1933 ዓ.ም እስከ 1947 ዓ.ም ድረስ፣ መጀመሪያ የጽሕፈት ሚኒስትር፤ ቀጥሎ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር፣ በመጨረሻም የጽሕፈትና የፍርድ ሚኒስትር በመሆን፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ለዐሥራ አራት ዓመታት በኢትዮጵያ የአስተዳደር ሕይወት ላይ የነበራቸውን ሥልጣንና የተጫወቱትን ሚና የምናነበው፤ የታሪኩን ሂደት ከጉዳዩና ከጊዜው ጋር እየተከተልን ስንሄድ ነው።

---

* የወልደጊዮርጊስ ልዩ ደብዳቤ ሉንዶን፤ እንደ ኢት.አቆ ሐምሌ 7 ቀን 1931 ዓ.ም

# ምዕራፍ ፫

## የሁለቱ ሰዎች ወዳጅነትና ለኢትዮጵያ ያላቸው ምኞት፤

ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያን ነፃነት ይዘው መናገሻ ከተማቸው በገቡ በአሥረኛው ቀን ለመጀመሪያ ጊዜ ባቋቋሙት ካቢኔያቸው፣ አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስን ጸሐፊ ትዕዛዝ ብለው የጽሕፈት ሚኒስትርነቱን ሲሾሟቸው፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድ በስደት ከሚኖሩበት ከፈረንሣይ አገር አዲስ አበባ አልተመለሱም ነበር። ስለዚህም፣ በ1934 ዓ.ም አገራቸው በተመለሱበት ጊዜ ንጉሠ ነገሥቱ አዘጋጅተው የጠበቋቸው ቦታ የእርሻና የደን ሚኒስትርነት ነው። ከጣልያን ጦርነት በፊት፣ አቶ መኰንን የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስቴርን ከበላይ ሚኒስትር ሳይሾምባቸው በዋና ዲሬክተርነት ብቻቸውን ይመሩት ስለነበረ፣ ከአምስት ዓመታት የስደት ዘመን በኋላ የተሰጣቸው ሚኒስትርነት ለእርሻው ጉዳይ ብቻ መሆኑ እንደ ትልቅ ሹመት ባይቆጠርም፣ አቶ መኰንን ቅሬታ አላሳዩም።

የኢትዮጵያ ነፃነት በተመለሰ በሁለተኛው ዓመት ሐምሌ 7 ቀን 1935 ዓ.ም፣ መኰንን ሀብተወልድ ከእርሻ ሚኒስትርነታቸው ጋር የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስቴርን አጣምረው እንዲመሩት ተሾሙ። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ ነሐሴ 20 ቀን 1935 ዓ.ም ደግሞ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስም የጽሕፈት ሚኒስትርነቱን እንደያዙ፣ የአገር ግዛት ሚኒስትርነቱን ደርበው ተሾሙ። ንጉሠ ነገሥቱ ለእነዚህ ለሁለቱ ታማኞቼ ናቸው ለሚሏቸው ሰዎች ለእያንዳንዳቸው ሁለት ሚኒስቴር እያደራረቡ በሾሟቸው ጊዜ፣ በፕሮቶኮል ረገድ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ከመኰንን ሀብተወልድ ቅድሚያ እንዲሰጣቸው አደረጉ። ከዚህ ቀደም ታሪኩ በትክክል እንደ አሳየን፣ ከጦርነቱ በፊት አቶ መኰንን ከወልደጊዮርጊስ የብዙ ዓመታት የሹመትና የፕሮቶኮል ቅድሚያ የነበራቸው ቢሆኑም፣ በአዲሱ አስተዳደር ንጉሠ ነገሥቱ ያደረጉትን የፕሮቶኮል ለውጥ፣ የንግድ፣ የእርሻና የኢንዱስትሪ ሚኒስትሩ የተቀበሉት በመልካም መንፈስ ነበር። በዚያን ጊዜ በአካባቢው የነበሩ አንዳንድ የቤተመንግሥቱ የቅርብ ሰዎች እንደተናገሩት፣ ወልደጊዮርጊስ ወዳጃቸው መኰንን በዕድሜም ሆነ በአገልግሎት፣ ከዚያም በላይ በሹመትና በኒሻን ስለሚበልጧቸው፣ በፕሮቶኮል የተሰጣቸውን ቅድሚያ ላለመቀበል ይቅርታ ጠይቀው ነበር። ለዚህ ማመልከቻ ከንጉሠ ነገሥቱ አንዳች መልስ ሳያገኙ፣ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ዙፋን አዳራሽ በተደረገ በአንድ ሥነ በዓል ላይ፣ ሻለቃ መርዕድ መንገሻ የግርማዊነታቸው ዋና የእልፍኝ አስከልካይ (ኋላ ሌፍትናንት ጀነራል) ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን እየመሩ ወስደው ከመኰንን ወንበር በላይ የተዘጋጀላቸውን ቦታቸውን ሰጧቸው። ከዚህ ዕለት በኋላ ይህን አዲሱን የፕሮቶኮል ሥርዓት ሁሉም በአክብሮት ከመቀበል በስተቀር፣ በየትኛውም ወገን ይኸ ለምን ተደረገ ? ይኸ ለምን ቀረ ? የሚል ትችት አልተሰማም። ይሁን እንጂ፣ እንደየሚኒስቴሮቹ የሥራ ክብደትና ኃላፊነት ሲታይ፣ የንግድ፣ የኢንዱስትሪና የእርሻ ሚኒስትሩን ከጸሐፊ ትዕዛዙና ከአገር ግዛት ሚኒስትሩ በፕሮቶኮል ማስቀደም ትክክል ነው ተብሎ የሚገመት አልነበረም። ያም ሆነ ይህ ገና ከጦርነቱ

በፊት ጀምሮ በሁለቱ ሰዎች መካከል የተሳሰረው መግባባትና ወዳጅነት በቀላሉ የሚፈታ ስላልሆነ፣ ከጊዜ ወደጊዜ እየጠነከረ ሄደ እንጂ ንፋስ አልገባበትም። ለዚህም አንዱ ማስረጃ፣ መኰንን ሀብተወልድ በጠላት ዘመን በስደት ከኖሩበት ከፓሪስ አዲስ አበባ ከተመለሱበት ዕለት ጀምሮ ለስድስት ወራት የኖሩት፣ ወዳጃቸው ወልደጊዮርጊስ በመኖሪያ ቤታቸው ውስጥ ባዘጋጁላቸው የተሟላ ማረፊያ ቤት ነበር። ከስድስት ወራት በኋላ፣ አቶ መኰንን አቡነ ጴጥሮስ ሐውልት አጠገብ የነበራቸውን ቤት አድሰውና ዕቃውን አሟልተው የወልደጊዮርጊስን ቤት ለቅቀው ቢወጡም፣ ሁለቱ ወዳጆች በቀን አንድ ጊዜ ለምሳ ወይም ለእራት መገናኘታቸውን አላቋረጡም። አንዳንድ የፖለቲካ ታዛቢዎች በሚሰጡት አስተያየት፣ ሁለቱ ባለሥልጣኖች ወዳጆቻቸውን ለማሳደግ ሆነ ወይም ደግሞ ተቃዋሚዎቻቸውን እየመነጠሩ ለማባረር፣ በጥሞና የሚመካከሩትና አስፈላጊውን እርምጃ የሚወስዱት በእነዚህ ለምሳ ወይም ለእራት ብቻቸውን በሚገናኙበት ጊዜ ነው እያሉ ይተቹ ነበር።

አፄ ምኒልክ በዘመነ መንግሥታቸው በሥልጣን እያሳደጉ ለመኳንንትነት ያበቋቸው እንደ ራስ ጉበና አባ ጥጉ፣ እንደ ፊታውራሪ ሀብተጊዮርጊስ (አባ መቻል) እና እንደ ራስ ተሰማ ናደው (አባ ቀማው) የመሳሰሉት ታላላቅ ሰዎች፣ እርስ በርሳቸው እየተከባበሩ በሰላም ከመኖር በስተቀር፣ በአባ ዳኘው ዘመን መሳፍንት ተነሥቶ ሥልጣን ይቀማናል በሚል ሥጋት በየፊናቸው ወገኖቻቸውን ለማስታጠቅ ሲሞክሩ አልታዩም። ለዚህ ሹመትና ደረጃ የመረጠን ጌታችን ምኒልክ ስለሆነ፣ መሳፍንት ተነሥቶ እንኳንስ ሊያጠፋን ሊያጠቃንም አይዳዳውም በማለት፣ ዕምነታቸውን በንጉሣቸው ላይ አሳርፈው የሚኖሩ ነበሩ። በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመን ግን፣ በአንድ በኩል መሳፍንትና መኳንንት፣ በሌላ በኩል ሥልጣኔንና ዘመናዊ ትምህርትን የቀመሱት የድሆች ተወላጆች፣ በዘውዱ ዙሪያ ተሰልፈው በሥልጣን የሚፎካከሩበት መንገድ ስለተከፈተ፣ በመጨረሻው የትኛው ወገን አሸናፊ ሆኖ ንጉሡን በመያዝ አገሪቱን እንደሚመራ አይታወቅም ነበር። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ግን፣ ምንም እንኳ የድሀውን ወገን እያስተማሩ ለከፍተኛ ሥልጣን በማድረስ ረዳቶቻቸው እንዲሆኑ ቢያደርጉም፣ መሳፍንትንና መኳንንትን ከዋና ዋናው የአገር አስተዳደር ሥልጣን እንዲርቅ ያድርጉት እንጂ፣ በዘውዱ አደባባይ ላይ እየተጉማለለ የሚይዘውን የፕሮቶኮል ወንበር አልነፈጉትም። ይህም ቢሆን መሳፍንቱ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ላይ ያሳደረውን ቅሬታ የሚያሻሽለው አልሆነም። " ..... አፄ ምኒልክ የአገልጋዮቻቸውን መብት በእኩል ደረጃ እየጠበቁ በማስተዳደራቸው፣ አገራችን ሰላምና ጤና ከማግኘት አላቋረጠችም ነበር። ዛሬ ግን የተፈሪ መኰንን ዋና ዓላማ፣ ኢትዮጵያን ወደ ፈረንጆች ሥልጣኔ እመራታለሁ በማለት፣ የመሳፍንቱንና የድሆቹን ተወላጆች እያናከሱ፣ አንደኛው የሌላው ጠላት ሆኖ ተንኮል ሲጭር እንዲያድርና፣ እሳቸው ደግሞ ማህል ቤት ዳኛ በመሆን እያተራመሱ በሥልጣን መጫወትን መርጠዋል። በዚህም ምክንያት ኢትዮጵያ አንድነቷ እየተፍረከረከ ከውጭ የሚሰነዘርባትን ጥቃት በሕዝቦቿ ኃይል ለመመከት የማትችል ለመሆን አብቅተዋታል። በንጉሥ ተፈሪ የከፋፍለህ ግዛ አመራር፣ ከዚህ ቀደም ለጠላታችን ለሙሶሊኒ ምን ያህል እንደረዳውና የኢትዮጵያ ሕዝብ ሳይዋጋ ለጠላት በሩን ከፍቶ በመገኘቱ ነፃነታችንን ለማጣት እንደበቃን መርሳት የለብንም። ዛሬም ንጉሡ ነገሥቱ ካለፈው ስሕተታቸው መማር ስላልፈለጉ፣ የኢትዮጵያን ሕዝብ እርስ በርሱ የሚያፋቅርና የሚያቀራርብ ተግባር ይፈጽማሉ ብለን ተስፋ እናደርግም ... " በማለት መሳፍንትና መኳንንት ምሬታቸውን ይገልጣሉ።

የሕዝብ ልጆች የሆኑት የድሆቹ ወገኖች ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ ደግሞ፤ አስተያየታቸውና ዕምነታቸው የተመሠረተው ከዚህ በሚከተለው መንፈስ ላይ ነው። " ...... ባለንበት ዘመን አገራችን ኢትዮጵያ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን የመሰለ መሪ በማግኘቷ ምን ያህል የታደለች መሆኗን ከልባችን እናምናለን። ኢትዮጵያን አሠልጥኖ ከዓለም ቤተሰብ ጋር ለማገናኘትና ነፃነቷን አስከብሮ ለመኖር፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ያቀዱት ሁሉ ከፍ ያለ ተስፋ የሚደረግበት የተቀደሰ ሥራ ነው። ይህንንም ግብ ለመቀዳጀት የሚያስችለው ትልቁ መፍትሔ ትምህርት መሆኑን በማመን፤ በያለበት ዘመናዊ ተማሪ ቤቶች ከፍተው የሕዝብ አልጋይዎች መሆን የሚችሉትን የነገዎቹን ፍሬዎች በማዘጋጀት ላይ ናቸው። በዚህ አኳኋን አገሪቱ የሚያስፈልጋትን ዘመናዊ የአስተዳደር ሥራ መረከብ ያለባቸው የሕዝብ ልጆች መሆናቸውን በማመን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የሚያደርጉትን ብርቱ ጥረት እንኳንስ ባለ ጉዳዮቹ የሆንነው እኛ ኢትዮጵያውያኖች ቀርተን፤ የሌላውም ዓለም ሕዝብ በጥልቀት እየተመለከተ አድንቋቸዋል።

> " ከትልቅ ተወልጃለሁ ማለት ሞያ አይደለም። በሚገባ ተምሮ ራስን ለትልቅ ደረጃ ማብቃት ግን፤ ከሁሉ የበለጠ የተከበረ ሞያ ነው። " ቀ.ኃ.ሥ

የሚለውን አስተሳሰብ በተማሪዎቹ አእምሮ ላይ እንዲቀረፅ፤ እየደጋገሙ የሚያደርጉት ንግግር፤ ለመሳፍንትና ለመኳንንት ቤተሰብ ሳይሆን የሕዝቡን ልጆች ለማትጋትና ለማስቀደም መሆኑን የሚስተው የለም። መሳፍንትና መኳንንት ለእኛ ለድሆቹ መብታችን እየተጠበቀ አገራችንን ለማገልገል የሚያስችለንን ሰላም እንድናገኝ አስበውልን አያውቁም። እነሱ ወደዚህ ዓለም የመጡት፤ መከራና ፈተና ሳያገኛቸው እጅግ በተሟላና በተመቻቸ ሕይወት እኛን ድሆቹን እየገዙ ለመኖር ነው። በእነሱ አስተያየት እኛ የተፈጠርነው እነሱን ለማገልገል ብቻ ሲሆን፤ እነሱ ደግሞ በእኛ ላይ ግፍ እየፈጸሙ መኖርን መብት አድርገው ቆጥረውታል። ዕድሜ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ! በአገራችን ላይ የሥልጣኔ ብርሃንን ስለፈነጠቀ፤ ከእንግዲህ ወዲህ የመሳፍንትና የመኳንንት አገዛዝ አይደርስብንም። መብታችንን የምናስከብርበትና ችሎታችንን ለአገር ጥቅም የምናውልበት ዕድል ተከፍቶልናል። ከእኛም ቀጥሎ የሚመጡት ልጆቻችን ትምህርታቸውን ሲጨርሱ፤ የአገር አስተዳደር ኃላፊነት ሥራ ተዘጋጅቶ ይጠብቃቸዋል። እኛም ይህንን እፊታችን የሚታየውንና እስከዛሬም ጥሩ ውጤት የሰጠውን ዕድላችንን ለመጠበቅ ከመቼውም ይበልጥ አንድነታችንን ማጠንከር አለብን። ከመሳፍንትና ከመኳንንት ቤተሰብ ጋር ያለን ውጊያ በቀላሉ የሚፈታ አይደለም። ከሁሉም ይበልጥ መሥጋት ያለብን፤ መሳፍንትና መኳንንት አብረው፤ አለኝታ መሪያችን የሆኑትን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን እንዳያጠፉብን ነው። በኢትዮጵያ መሻሻልና በድሆች ልጆች የሥልጣን ዕድገት እጅግ የተበሳጩ በመሆናቸው፤ መሳፍንት አንድ ቀን ልብ አግኝተው በተፈሪ መኰንን ላይ አደጋ ጥለው ቢገድሏቸው፤ ውርሱ የኛ ነው በማለት፤ የአገሪቱን መሪነት ለመረከብ አቅም ያላቸው እነሱ መሆናቸውን መዘንጋት የለብንም። ዛሬ በአለንበት ሰዓት ኃይላችንና መከታችን ተፈሪ መኰንን ብቻ ናቸው። እሳቸውን ብናጣ፤ መሳፍንትን ተቋቁሞ ለመጣልና አገራችንን ከፊውዳሎች እጅ ለማዳን የሚያስችል ዕድል እንደሌለን ለማንም ግልጽ ነው። ሕዝባችንም የሠለጠነው ዓለም የደረሰበትን የዴሞክራሲ ሥርዓት ለመረዳት በአሁኑ ሰዓት ስለማይችል፤ ንጉሥ ቢሞት ንጉሥ ለመተካት አስፈላጊውን ምክርና ውሳኔ የሚቀበለው ከመሳፍንት እንጂ ከእኛ ወገን አይደለም። ስለዚህ፤ ሳንቀደም

ቀድመን መገኘት አለብን። ይኸውም፣ ለኢትዮጵያ መድህን የሆኑትን መሪያችንን ሌት ተቀን እንደ ዘብ ቆመን መጠበቅና፣ በእሳቸው መሪነት ለአገራችን የተጀመሩትን የትምህርትና የአስተዳደር መሻሻል ዕቅዶች በፍጥነት እንዲራመዱ ጊዜውን መሻማት ነው ..... "

ከዚህ በላይ የተገለጸው የሐሳቡ ሥዕል የሚያመለክተው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ገና ከአልጋ ወራሽነት ዘመናቸው ጀምሮ በየደረጃው ለከፍተኛ ኃላፊነት ያበቋቸው ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ፣ በዘውዱ ሐረግ ውስጥ የሚገኙት መሳፍንት ከተባበሩና ከቆረጡ፣ የድሆች ወገን የሆኑትን ተፈሪ መኰንንን አጥፍተው የዘውዱ ወራሽ ለመሆን የሚያስችል አቅም አላቸው በማለት ያደረባቸውን ሥጋት ነው። በእርግጥ እንደተባለውም፣ የድሆች ወገኖች ወደ ሥልጣን ሲገሰግሡ፣ መሳፍንትና መኳንንት በያለበት ምሬታቸውን ከማሰማት፣ ብልህነትና ዘዴ ቢኖራቸው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን በስውር ጉዳና አጥፍተው የዘውዱን የወራሽ መስመር መለወጥ ይችሉ ነበር። ነገር ግን፣ ድፍረትና ቆራጥነት ስላልነበራቸውና ማመንታት ስለአጠቃቸው፣ ምኞታቸውን ሳይጠቀሙበት እንዲሁ በያለበት እሮሮ በማሰማት ብቻ ዘመናቸውን ጨርሰውታል።

መሳፍንትን ከታላላቅ የመንግሥት ሥራ ኃላፊነት ማራቅና የሕዝብ ወገኖችን ለሥልጣን ማብቃት፣ ለዘመናዊት ኢትዮጵያ እጅግ ጠቃሚነቱን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተገነዘቡት ቢሆንም፣ በሌላ በኩል ደግሞ የንጉሠ ነገሥትነት ሥልጣናቸውን እንደልባቸው ለመጠቀም፣ ከመሳፍንቱ ይልቅ፣ የድሆቹ ወገኖች ምን ያህል ምቹ እንደሆኑላቸው በግልጽ የሚታይ ነው። በዚህ አኳኋን ተፈሪ መኰንን የድሆቹን ወገኖች ለማስተማርና ለአገር ኃላፊነት ደረጃ ለማድረስ ያደረጉት ጥረት፣ በመጨረሻው የሕይወት ዘመናቸው የድሆች ልጆች ሙሉ ሥልጣን ከያዙ በኋላ በሕይወታቸው ፍጻሜ ላይ ያደረሱባቸው ጭካኔ የሚያሳዝን ቢሆንም፣ ከመሳፍንት ወገን የጠነከረ የተቀናቃኝ ኃይል ሳይገጥማቸው፣ ጥቃትም ሳያገኛቸው፣ ለዐርባ አራት ዓመታት የንጉሠ ነገሥት ሥልጣናቸውን የሠሩበት መሆኑን መዘንጋት አይቻልም።

# ምዕራፍ ፬

# የገጠሩን ሕዝብ ከመንግሥት ጋር ለማቀራረብ

የፋሽስት ጣልያን ከኢትዮጵያ ከተባረረ በኋላ፣ እ.ኤ.አ ከ1943 እስከ 1955 ዓ.ም ድረስ ለአሥራ ሁለት ዓመታት የኖረው የወልደጊዮርጊስና የመኰንን ሀብተወልድ የአንድነት ሥልጣን ኃይል የተመሠረተው፣ እኛ የድሆች ወገኖች ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ይዘን፣ የአገራችንን አስተዳደር ከፌዎዳል መሳፍንት ፍጹም ነፃ በማድረግ፣ ኢትዮጵያን ከፍ ያለ የሥልጣኔ ደረጃ ላይ እናደርሳታለን በሚል አስተሳሰብ መሆኑን ባለፈው ምዕራፍ በሰፊው ተገልጿል።

ተፈሪ መኰንን፣ እነዚህን ሁለት የቡልጋ ተወላጆች ያወቋቸውና ባለሟል ያደረጓቸው፣ በብልህነታቸውና በትጋታቸው መርጠው ሲሆን፣ እነሱም የተዋደዱትና አንድነታቸውን ያጠናከሩት፣ የመሳፍንት ጥቃት በራሳቸውም ሆነ በወገኖቻቸው ላይ እንዳይደርስባቸው ለመከላከል መሆኑን ደህና አድርጐ ያልተገነዘበ የለም። እነዚህ ሰዎች በመሳፍንቱና በመኳንንቱ ዘንድ የተጠሉ መሆናቸው የታወቀ ቢሆንም፣ በየተሾሙበት ሚኒስቴር አስተዳደራቸው በከፍተኛ ዲስፕሊን ላይ የተመሠረተና ብርቱ ቁጥጥር የሚያደርጉ በመሆናቸው፣ በአብዛኛዎቹ ሠራተኞቻቸው ዘንድ የተወደዱ አልነበሩም። ይሁን እንጂ፣ እንደ ድፎ ዳቦ ከበላዮቻቸው ሆነ ከበታቾቻቸው የጥላቻ እሳት የሚነድባቸው፣ ለአገሪቱ ዕድገት ጠቃሚ የሚሆነውን በጃንሆይ ስም ለመሥራትና ንጉሠ ነገሥቱም በሕዝባቸው ዘንድ ተወዳጅ እንዲሆኑ ለማስደረግ እንጂ ለግል ጥቅማቸው ስላልሆነ፣ ተፈሪ መኰንን በእነዚህ በሁለቱ አገልጋዮቻቸው ላይ ሙሉ ዕምነት ከማሳረፍ በስተቀር፣ የሚጠራጠሩበት ሆነ የሚሠጉበት ነገር አልነበራቸውም።

"እነዚህ አንደኛው ከቤተክርስቲያን ደብተራ፣ ሌላው ከእጅ ሥራ ሞያተኛ የተወለዱ ሰዎች፣ በምን የተነሣ በሥልጣን እናታችን ላይ ወጥተው ይጨፍሩብናል?" በማለት፣ መሳፍንትና መኳንንት እንደዚያ ሲነቅፏቸውና ሲሰድቧቸው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ሕግ ፊት አስቀርበው እንዲቀጡ ባያደርጉም፣ ከስድብ አልፈው በሁለቱ ታማኝ አገልጋዮቻቸው ላይ አደጋ ለማድረስ እንዳይሞክሩ በልዩ ዘብ ያስጠብቋቸው ነበር። በዚህም በሚደረግላቸው ጥበቃ በመተማመን፣ ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ በመሳፍንትና በመኳንንት ላይ ትከሻቸውን ከፍ እያደረጉ በተሰጣቸው ሥልጣን የሚፈልጉትን ሁሉ ከመሥራት ወደ ኋላ አላሉም። እነሱ መርጠው ያቀረቡት ካልሆነ በስተቀር፣ ሚኒስትር ሆነ ምክትል ሚኒስትር፣ ዋና ዲሬክተር ሆነ ዋና ጸሐፊ፣ የንጉሠ ነገሥቱ ሹመት አይሰጠውም። የወልደጊዮርጊስና የመኰንን ምርጫ አስፈላጊ ያልሆነው፣ ለጠቅላይ ግዛቶችና ለአንዳንድ ዋና ዋና አውራጃዎች በሚሾሙት ገዥዎች ጉዳይ ብቻ ነበር። በእነዚህ ሹመቶች፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከመወሰናቸው በፊት የዋናዎቹን መሳፍንት አስተያየት ያዳምጣሉ። ለምሳሌም ያህል፣ ራስ ሥዩም ለትግራይ፣ ራስ ብሩ ለከፋ፣ ራስ ኃይሉ በለው ለጐጃም፣ ራስ አደፍርሰው ለሲዳሞ፣ ቢትወደድ አንዳርጋቸው ለጐንደር ገዥነት ሲደለደሉ፣ እነ ወልደጊዮርጊስ የሰሙት፣ የሹመቱ አዋጅ

በሲጋባው ሲዘጋጅ እንጂ ሐሳቡ ሲፀነስ አልነበረም። እነሱም በዚህ አሠራር ቅሬታ አላደረባቸውም። ንጉሠ ነገሥቱ ለየክፍለሀገሩና ለየአውራጃው የሚመድቧቸውን ገዥዎች፣ ከመሳፍንትና ከመኳንንት ጋር መመካከራቸውንና አብዛኛዎቹንም ተሿሚዎች ከእነሱ መካከል መምረጣቸው የተገባ መሆኑን ያምኑበታል። በዚያን ዘመን (1933-1947) መሳፍንትና መኳንንት፣ በየክፍለ ሀገሩ በያዙት ቁጥሩ ወሰን በሌለው ርስትና ርስተ ጉልታቸው ላይ የሰፈረውን ሕዝብ የሚገዙት በሚያስመርር የገባር ጭቆና ሥርዓት ቢሆንም፣ ዘውዱንና አካባቢውን የሚነካ አንድ ዓይነት ለውጥ ለማፈንዳት ሙከራ ቢደረግ፣ አብዛኛው የፊውዳል አገዛዝ ተጭኖት የኖረው ሕዝብ፣ ጥንታዊ ልማዱን በመከተል ለመሳፍንት ገዥዎቹ አለሁ ብሎ እንደሚቆምላቸው መረሳት የለበትም። ስለዚህ፣ ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ ሥልጣን በእጃቸው በሆነበት ዘመን፣ የሕዝቡን ድጋፍ አግኝተው መሳፍንትን ከየርስቱ ለመንቀልና የገባር ጭቆናን አስተዳደር በቀላሉ ለመደምሰስ ይቻላል ብለው የሚያልሙ አልነበሩም። የእነሱ ተስፋና ምኞት፣ በቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት በተገኘው ዕድል የድሆች ልጆች እየተማሩና እየሠለጠኑ በየመስኩ ያለውን የአገሪቱን አስተዳደር ኃላፊነት በሚረከቡበት ጊዜ፣ ሕዝቡን ከመሳፍንት አገዛዝ ለማላቀቅና ኢትዮጵያን ለማልማት ይቻላል በሚል አስተሳሰብ ላይ የተመሠረተ ነው። ይህንንም ግብ ለመቀዳጀት፣ የወልደጊዮርጊስና የመኰንን ጥረት ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ ከሁሉ በፊት ቅድሚያ የሚሰጡት፣ ንጉሠ ነገሥቱ የጀመሩትን የአስተዳደር መሻሻል በሰላም ለመቀጠል እንዲችሉ፣ ደህንነታቸውን መጠበቅና በሚሠሩት ሥራ ሁሉ በመላው ሕዝባቸው ዘንድ ተወዳጅነትን እንዲያገኙ ማድረግ ነው።

ወልደጊዮርጊስ በጽሕፈት ሚኒስትርነታቸው የንጉሠ ነገሥቱ አፈ ጉባኤ በመሆን በያዙት ከፍተኛ ሥልጣን፣ ለአገሪቱ ዕድገትና መሻሻል የሚያስፈልገውን ሁሉ እያቀረቡ ማስፈጸም ዋናው ተግባራቸው ሲሆን፣ ደርበው በያዙት በአገር ግዛት ሚኒስትርነታቸው ደግሞ ፖሊሱንና የፀጥታ መረጃውን በእጃቸው በማድረግ የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት ደህንነት ለመጠበቅ አስችሏቸዋል። አገረ ገዥዎች በጥንታዊው ሥርዓት እንደነበረው፣ የመሬት ግብርና አሥራት ከሕዝቡ ላይ እየሰበሰቡ ለሕይወታቸው ምቹት ቅድሚያ በመስጠት የሚፈጽሙት ፊውዳላዊ የግፍ አሠራር እንዲቀርና፣ እያንዳንዱ ጠቅላይ ግዛት የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት በሚወስንለት በጀት ብቻ እንዲተዳደር የሚያስፈልገውን አዋጅ በማዘጋጀትና በማስከበር ረገድ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ያሳዩት ጥንካሬ እጅግ ተደንቆላቸዋል። ይህ አዋጅ፣ ሕዝቡን ከጭቆና አስተዳደር ነፃ ለማድረግ ከፍ ያለ ዕድል የከፈተ ነው ተብሎ በአዲስ አበባ በሰፊው ቢነገርም፣ ተጠቃሚው አርሶ አደሩ ሕዝብ ንጉሠ ነገሥቱ ያሰቡለትንና ያደረጉለትን እርዳታ እንዲገነዘበው ለማስደረግ፣ በዚያን ዘመን ያለው የፕሮፓጋንዳ ሥራ ማሠራጫ ድርጅት ይህን ያህል የሚያጠግብ አልነበረም።

የኢትዮጵያ ነፃነት ከፋሽስት ቀንበር ከተላቀቀ ወዲህ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባቋቋሙት በአዲሱ መንግሥታቸው ውስጥ የማስታወቂያና የጋዜጦች መሥሪያ ቤትን የጽሕፈት ሚኒስትራቸው ቀጥታ እንዲመሩት ስለአደረጉ፣ በወልደጊዮርጊስ ላይ የወደቀው የፕሮፓጋንዳ ኃላፊነት እጅግ የከበደ ነበር። በዚህ በጋዜጣና ማስታወቂያ መሥሪያ ቤት በየሳምንቱ ቅዳሜና ሮብ በሚታተሙት አዲስ ዘመንና ሰንደቅ ዓላማችን በተባሉት ጋዜጦች ላይ፣ ንጉሠ ነገሥቱና መንግሥታቸው ለአገሪቱ ዕድገትና ለሕዝቡ ሥልጣኔ የሚያቅዱትንና የሚወስኑትን ከዝርዝር ሐተታ ጋር ቢታተምም፣ እነዚህን ጋዜጦች ከታላላቆቹ በስተቀር ለገጠሩ ሕዝብ

ለማዳረስ አልተቻለም። የፋሽስት መንግሥት የኢትዮጵያን ሕዝብ ለመስበክ አዲስ አበባ ላይ ያቋቋመው አንድ ኪሎዋት ተኩል የሆነው የራዲዮ ጣቢያም ከአቅሙ ማነስ የተነሣ፤ ከአዲስ አበባ ውጭ በጣት ከሚቆጠሩ ከጥቂቶች ከተሞች በስተቀር፤ ለየአውራጃው ነዋሪ ሕዝብ ማሰማት አይችልም ነበር።

በዚህ ሁኔታ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በየጊዜው ለአገር አስተዳደርና ለሕዝብ ኑሮ መሻሻል የሚወስዷቸውን እርምጃዎች ለሕዝቡ ለማስረዳት፤ በዘመኑ ያሉት የጽሑፍና የቃል ፕሮፓጋንዳ ማሠራጫዎች የሚያረኩ ባለመሆናቸው፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድ አንድ የተለየ ሐሳብ አቀረቡ። ይኸውም፤ በየአውራጃዎቹ ከሚገኙት ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች* መካከል፤ የተፈጥሮ ብልህነትና የማስረዳት ችሎታ ያላቸው እየተመረጡ፤ አዲስ አበባ እንዲመጡና ለአገር አስተዳደር ዕድገትና ለሕዝባቸው ኑሮ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው እያሰቡ፤ ከጠላት መባረር በኋላ እስከዛሬ ድረስ ያወጧቸው አዋጆች ሁሉ፤ ዓላማቸውና ግባቸው ምን መሆኑን በጥልቀት እንዲያጠኑት ከተደረገ በኋላ፤ ወደየግዛታቸው ተመልሰው ለሕዝቡ እንዲያስረዱ ማድረግ ጠቃሚ ይሆናል የሚል ነበር። የዚህን ሐሳብ ጠቃሚነትና አስፈላጊነት በመጀመሪያ ተረድተው እጅግ የተደሰቱት ወልደጊዮርጊስ ሲሆኑ፤ ንጉሠ ነገሥቱም በተግባር ይገለጽ ብለው መልካም ፈቃዳቸውን ለመስጠት ውለው አላደሩም።

በዚህ መሠረት ለመጀመሪያው ጊዜ ከዋና ዋናዎቹ አውራጃዎች ውስጥ፤ ሐያ አምስት (25) ምስለኔዎችና (25) ጭቃ ሹሞች ተመርጠው አዲስ አበባ በመምጣት፤ ወልደጊዮርጊስ በሚመሩት በአገር ግዛት ሚኒስቴር ግቢ ውስጥ፤ ድንኳን የለበሰ ሰፊ አዳራሽ ተዘጋጅቶላቸው የሦስት ሳምንታት የትምህርት ፕሮግራም ሲከታተሉ ሰነበቱ። በመጀመሪያው ሳምንት ፕሮግራማቸው ላይ፤ የአገር ግዛት ሚኒስትሩ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤ ስለ አገር አገዛዝና አስተዳደር መሻሻል እስከ ዛሬ የተከናወነውንና ወደፊት የታቀደውን፤ የእርሻ ሚኒስትሩ አቶ መኰንን ሀብተወልድ በኢትዮጵያ የርሻ ልማት እየተስፋፋና የደን ሀብት እየተጠበቀ ሲሄድ፤ ለአገር ጥቅም ለማዋል ስለሚቻልበት ሁኔታ፤ የገንዘብ ምክትል ሚኒስትሩ አቶ ይልማ ዴሬሣ፤ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት መሥሪያ ቤቶችና ሠራተኞቹ በሠለጠነው ዓለም እንደሚደረገው በበጀት እንዲተዳደሩ ሲወስን፤ ሕዝቡ ለመንግሥት ገቢ የሚያደርገው፤ የግብርና የታክስ አከፋፈል አሠራሩ እንዴት እንደሆነ፤ የሚሰጡትን መግለጫዎች ማዳመጥ ነበር።

በሁለተኛውና በሦስተኛው ሳምንታት ውስጥ ለመልዕክተኞቹ የተሰጡት ጥናቶች፤ ንጉሠ ነገሥቱ ለኢትዮጵያ ዘመናዊ አስተዳደርና ለሕዝባቸው ሕይወት መሻሻል በማሰብ፤ በአዋጅ ስለገለጿቸው ዋና ዋና ጉዳዮች ነበር።

1ኛ/ ኢትዮጵያ በአሥራ ሁለት ጠቅላይ ግዛቶች እንድትከፈል የተደረገው፤ ዘመናዊውን አስተዳደር ለመከተል የሚያመች እንዲሆን በማሰብ ስለሆነ፤ በዚህ አሠራር ሕዝቡ በጐሣና በዘር ልዩነት ተጠንቶ የተደረገ መስሎ እንዳይታየው በሚገባ ማስረዳት፤

2ኛ/ እያንዳንዱ ጠቅላይ ገዥ የሚሾመው በንጉሠ ነገሥቱ መልካም ፈቃድ ሲሆን፤ ለግዛቱ ማስተዳደሪያና ለሠራተኞቹ ደሞዝ፤ መንግሥት በየዓመቱ በጀት

---

* ምስለኔ ማለት በመንግሥት የሚሾም የወረዳ ም/ገዥ ሲሆን፤ ጭቃ ሹም ደግሞ ነዋሪው ሕዝብ ተጠሪው አድርጉ የሚመርጠው ነው።

እየተመነ ስለሚመድብለት፤ ከእንግዲህ ወዲህ ሕዝቡ የመሬት ግብሩንና ማናቸውንም ታክስ የሚከፍለው ቀጥታ ለንጉሠ ነገሥቱ ግምጃ ቤት እንጂ፤ ቀድሞ ሲሠራበት እንደነበረው ለአገረ ገዥው አለመሆኑን በትክክል እንዲረዳው ማድረግ፤

3ኛ/ የሚሾመው ገዥ ለተሾመበት ጠቅላይ ግዛት ስለ አገር አገዛዝ የተሰጠውን ደንብና ሥርዓት ተከትሎ ሕዝቡን ከማስተዳደር በስተቀር፤ በአካባቢው ከሚገኙት የውጭ አገሮች ጋር የሚያዋስነውን ድንበር መጠበቅና ወራሪም ከመጣ ተዋግቶ ወሰኑን ማስከበር፤ ኃላፊነቱ ለንጉሠ ነገሥቱ የጦር ሚኒስትር ስለተሰጠ፤ ከእንግዲህ ወዲህ ይህን የመሰለው ጉዳይ ጠቅላይ ገዥውን የሚመለከት አለመሆኑን፤ ሕዝቡ እንዲያውቀው ማድረግ፤

4ኛ/ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ዋና ዓላማ ወደፊት በባለርስትና በአራሹ ገበሬው መካከል የሁለቱም ወገኖች መብት በትክክል የሚጠበቅበትን ሕግ ማውጣት ስለሆነ፤ ይህ አዋጅ ተሰናድቶ እስከሚገለጥበት ጊዜ ድረስ፤ በተለይ ገበሬው ሕዝብ በተስፋና በትዕግሥት እንዲጠባበቅ መንገር፤

5ኛ/ የሠለጠነው ዓለም የሚጠቀምበት "ትራክተር" የተባለው የእርሻ መኪና በብዛት ወደ አገራችን ገብቶ ከፍ ያለ ጥቅም እስከሚሰጥበት ጊዜ ድረስ፤ በኢትዮጵያችን ልማድ ቀንበር ተሸክሞ ሞፈር እየጐተተ የሚያርሰው በሬ፤ ድካሙ የሚቃለልበትና የተሻለ ውጤት የሚሰጥበት መንገድ ይፈለግለት ብለው ንጉሠ ነገሥቱ ስለአዘዙ፤ የእርሻ ሚኒስቴር አስፈላጊውን በማድረግ ላይ ይገኛል። ይኸውም፤ እስከዛሬ ገበሬው የሚጠቀምባቸው ማረሻዎች ሁሉ "ዱልዱም" በመሆናቸው፤ ጫፋቸው እየተሳለ መሬቱን በቀላሉ ለመቀርደድ (ለማረስ) እንዲችሉ፤ በየጠቅላይ ግዛቱ ዋና ዋና ከተሞች የእርሻ ሚኒስቴር ለገበሬዎች የቴክኒክ እርዳታ የሚሰጡ ጣቢያዎች ለማቋቋም ተዘጋጅቷል። ስለዚህ፤ በቅርብ ጊዜ ውስጥ ገበሬዎች እስከዛሬ ሲጠቀሙበት የቆዩትን ዱልዱም ማረሻዎቻቸውን ለእርሻ ሚኒስቴር ጣቢያ እያቀረቡ በነፃ እንዲሳሉላቸው ለማድረግ መቻላቸውን ማስረዳት፤

ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፤ ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ ኢትዮጵያን ለማሻሻል ንጉሠ ነገሥቱ የሚያደርጉት ጥረት በሕዝባቸው ዘንድ እንዲታወቅላቸውና ሕዝቡም ነገሩን ተረድቶ በተቀየሰለት መንገድ እየተጓዘ እንዲጠቀም በማሰብ፤ ከየአውራጃው የተወሰኑ ምስለኔዎችንና ጭቃሹሞችን አዲስ አበባ ሰብስበው የሰጧቸው ትምህርት እና የጣሉባቸው አደራ፤ በመጨረሻ እንደታየው የተመኙትንና የጠበቁትን ውጤት ሳይሰጥላቸው ቀረ። የዚህን አሠራር ሐሳብ ያመነጩት መኰንን ሀብተወልድና ሙሉ ድጋፋቸውን የሰጡት ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ፤ በዚያን ጊዜ ለእነሱ የታያቸው፤ በየግዛቱ ያሉት ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች ምንም እንኳ፤ ነዋሪውን ሕዝብ የሚያስቸግሩና የሚያንገላቱ ናቸው እየተባሉ በልማድ እየተወቀሱ የሚኖሩ መሆናቸው ቢታወቅም፤ ከሕዝቡ የዕለት ሕይወት ጋር ቅርበትና የዘወትር ግንኙነት ያሏቸው ስለሆኑ፤ አዲስ አበባ መጥተው በሚገባ ከተመከሩና እንዲዘጋጁ ከተደረገ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ዓላማና ዕቅድ ሕዝቡ እንዲያውቅ ለማድረግ ከእነሱ የተሻለ ሌላ አይኖርም በማለት ነበር። ነገር ግን ይህ ዓይነቱ አሠራር ከዚህ ቀደም እንኳንስ በኢትዮጵያ፤ በሠለጠነውም ዓለም ቢሆን፤ አገረ ገዥዎችን ከጉዳዩ በማራቅና ችላ በማለት፤ ከጭፍሮቻቸው ጋር ተወያይቶ እርምጃ መውሰድ የተለመደ አይደለም።

እርግጥ ነው! እነዚህ የጃንሆይ የቅርብ ታማኞች ይህንን አጥተውት አይደለም። በዚያን ዘመን የነበሩት ጠቅላይ ገዥዎች የአገር ግዛትና የእርሻ ሚኒስትሮቹ እንኳንስ የሚልኩላቸውን መምሪያዎች ተቀብለው ለመፈጸም ይቅርና፣ የሚገልጹላቸውንም አንዳንድ አስተያየቶች ለማዳመጥ እንኳን ፈቃደኞች አልነበሩም። ስለዚህ፣ አገረ ገዥዎቹን እንደሌሉ ቆጥሮ፣ ጭፍሮቻቸው የሆኑትን ምስለኔዎች እያስተማሩ ሕዝብን ከመንግሥት ጋር በማቀራረብ፣ ፌዎዳላዊ የሆነውን አሠራር ለማዳከምና በመጨረሻም ለመደምሰስ ይቻላል ብለው መኮንን እና ወልደጊዮርጊስ የቀየሱት ፕላን፣ በጊዜው ከነበረው ሁኔታ ጋር ሲመዘን እጅግ የፈጠነ እንደነበረ ለመረዳት አያዳግትም። ስለዚህም፣ የተወሰደው እርምጃ ውጤት ሳይሰጥ መቅረቱ የሚያስደንቅ አይደለም። አገረ ገዥዎቹ፣ የንጉሡ ነገሥቱ እንደራሴዎችና አፈ ጉባኤዎቹ እኛ ሆነን፣ የአገር ግዛትና የእርሻ ሚኒስትሮቹ ከዝቅተኞቹ ጭፍሮቻችን ጋር ግንኙነት እየዘረጉ የሚሠሩትን ተንኮል አንቀበልም የሚል አቋም ያዙ። ምስለኔዎቹም ከአዲስ አበባው ስብሰባቸው በኋላ፣ ብዙ ነገሮችን ተምረናል፣ መንግሥታችንም አክብሮ ከሕዝብ ጋር የመገናኛ ድልድዮች ሆነን እንድንሠራ ኃላፊነት ጥሎብናል በማለት፣ እየፈነደቁ ወደ ግዛታቸው ሲመለሱ፣ አለቆቻቸው በቁጣ እራስ ነብር ሆነው ስለጠበቋቸው፣ የአዲስ አበባውን ትምህርት በተግባር ለማዋል የማይቻላቸው ሆነ። ከምስለኔዎቹ መካከል አንዱ ጀግና መስሎ ለመታየት ስለፈለገ፣ ከመንግሥት የተሰጠኝን መልዕክት ለሕዝቡ ለማድረስ ማን ይከለክለኛል ? ብሎ ሲፎክር ስለተሰማ፣ ጠቅላይ ገዥው "ሥልጣኔን ተዳፍረሃል" በማለት በአደባባይ ሊገርፉት ሲወስኑ፣ አማላጆች ተደራርበው በመለመን አዳኑት። ይህ ሁኔታ ከደረሰ በኋላ፣ እነዚህ ተምረው የተመለሱት መስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች ያው እንደቀድሞአቸው የገዥዎቻቸውን ትዕዛዝ እጅ ነሥቶ ከመቀበልና ከመፈጸም በስተቀር፣ ከአዲስ አበባ የተሰጣቸውን መምሪያ እንኳንስ ሊሠሩበት ይቅርና ስብሰባው የተካሄደው በምን አኳኋን እንደነበረ ለወዳጆቻቸው ለማውጋት እንኳ ፍርሃት አድሮባቸው እንደበታቸውን መዝጋት ግዴታ ሆነባቸው።

የምስለኔዎቹ ስብሰባ በተካሄደ ጊዜ፣ የታወቁት መስፍን ልዑል ራስካሣ ለጠበል ከአዲስ አበባ ውጭ ሄደው ስለነበረ፣ ስለ ጉዳዩ የሰሙት አዲስ አበባ በተመለሱ ጊዜ ነው። ወልደጊዮርጊስና መኮንንም የራስ ካሣ አዲስ አበባ አለመኖር ያቀዱትን ለማከናወን ነፃ ሜዳ እንደሰጣቸው በመቁጠር ተደስተው ነበር። ሆኖም ልዑል ራስ ሲመለሱ፣ የተፈጸመውን ሁሉ በሰሙ ጊዜ አስተያየታቸውን ሳይሰጡ በዝምታ ማለፍ አልፈለጉም። " ... እረ ለመሆኑ ንጉሥ መርጦ የሾመው አገረ ገዥ እቦታው ላይ ቁጭ ብሎ፣ መንግሥት ለሕዝቡ መልካም አኗኗር የሚያስበውንም ሆነ ለመሥራት ያቀደውን፣ እታች ወርዶ ከምስለኔዎችና ከጭቃ ሹሞች ጋር መምከር ከየት የመጣ ልማድ ነው ? ......" ሲሉ ራስ ካሣ ላቀረቡት ጥያቄ፣ ወልደጊዮርጊስና መኮንን ሀብተወልድ መልስ እንዲሰጡ ከጃንሆይ ቢታዘዙም፣ ከፍርሃት የተነሣ ልዩ ልዩ ምክንያቶች እየፈጠሩ መስፍኑን ሳያነጋግሩ ሰንብተው ነበር። አንድ ቀን አቶ መኮንን ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት ከሚገኘው ከጃንሆይ ቢሮ ሲወጡ፣ ልዑል ራስ ካሣን ከቤተመንግሥቱ መግቢያው ላይ አገኟቸው። አቶ መኮንን በወጉ እጅ ከነሡ በኋላ ሹልክ ብለው ለማምለጥ ሞክረው ነበር። ነገር ግን፣ መስፍኑ እንደዚህ በቀላሉ አልለቀቋቸውም። ና ላነጋግርህ ! ብለው ጠሯቸው። በዚያ በገነተ ልዑል ቤተመንግሥት እንግዳ ማረፊያ ሳሎን ውስጥ ከልዑል ራስ ካሣ ጋር የተለዋወጧቸውን ንግግሮች አቶ መኮንን ለወንድሞቻቸው አጫውተዋቸው ስለነበረ፣ የዚህ መጽሐፍ ደራሲ ከአቶ አካለወርቅ ሀብተወልድ ያገኘውን ማስታወሻ እንደሚከተለው ያቀርባል።

ራስ ካሣ እንተንና ጸሐፊ ትዕዛዝን ለማነጋገር ፈልጌ መልዕክት ልኬባችሁ ነበር። ጃንሆይም ሳይነግሩዋችሁ አልቀሩም። በምን የተነሣ ችላ ብላችሁኝ ሰነበታችሁ ?

መኰንን ሀ.ወ የለም ! ልዑል ጌታችንን ችላ ብለን አይደለም። ጸሐፊ ትዕዛዝም እኔም ብዙ ሥራ ላይ ተጠምደን ስለሰነበትን፤ ጊዜ አጥሮን ነው።

ራስ ካሣ ስለ አገር ጉዳይ ለመወያየት በየግዛቱ የሚገኙትን የተመረጡ ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች አዲስ አበባ አስመጥታችሁ ከእነሱ ጋር ባደረጋችሁት ስብሰባ ብዙ ሥራ ተጭኗችሁ እንደነበረ እኔም ሰምቻለሁ። ለመሆኑ ያንን ያህል የደከማችሁበት ጉዳይ ምን ፍሬ እንዳመረተላችሁ ባጭሩ ልትነግረኝ ትችላለህ ? ...

መኰንን ሀ.ወ ልዑል ጌታዬ እንደሚያውቁት፤ በየአውራጃው ያሉት ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች የኔ ቢጤ ከሆነው ከተራው ሕዝብ ጋር በሥራም በኑሮም የዕለት ግንኙነቶች ስላሏቸው፤ የግርማዊነታቸው መንግሥት የሕዝቡን ኑሮ ለማሻሻል በልማትና በአስተዳደር በኩል የሚያወጣውን ደንብና ሥርዓት በትክክል እንዲረዱትና እነሱም በበኩላቸው በየግዛታቸው ለሚኖረው ሕዝብ በሚገባ ለማስረዳት እንዲችሉ አሠራሩን ካስጠናናቸው በኋላ፤ ወደየአገራቸው ተመልሰዋል። እነዚህ ሰዎች ያስተማርናቸውን ሁሉ ምን ያህል በተግባር እንደገለጹት እና ምን ያህል ፍሬ እንደሰጠ መገመት የሚቻለው ወደፊት ነው እንጂ፤ ባጭር ጊዜ ውስጥ ምርቱ ይታያል ብለን እኛም አንጠብቅም።

ራስ ካሣ፤ ታዲያ ! ይኸ አንተ የኔ ቢጤ ..... ተራ .... የምትለውን ሕዝብ ለማስተዳደር ንጉሥ መርጦ የሾማቸውን አገረ ገዥዎች ከዚህ እናንተ ካሰባችሁት መልካም ሥራ ለምን አገለላችኋቸው? ....

መኰንን ሀ.ወ አላገለልንም። እንዲህ የመሰለውን ሥራ ጨርሶ አናስበውም። ልዑል ጌታዬ እንደሚያውቁት፤ ጃንሆይ ለአገራችን የአስተዳደር መሻሻልና ለሕዝባቸው ደህንነት በየጊዜው የሚያቅዱትን ሐሳብና የሚያወጧቸውን አዋጆች፤ አገረ ገዥዎች በቅድሚያ እንዲያውቁትና እነሱም በበኩላቸው ለሚያስተዳድሩት ሕዝብ እንዲያስረዱ፤ መምሪያ ከመስጠትና አደራ ከማለት ያቋረጡበት ጊዜ የለም። ነገር ግን፤ እስከዛሬ ሲሠራበት እንደቆየው ልማድ ከሆነ፤ ጠቅላይ ገዥዎቹ ለየአውራጃ ገዥዎች፤ የአውራጃ ገዥዎች ደግሞ ለየወረዳ ገዥዎች፤ የወረዳ ገዥዎች ደግሞ በበኩላቸው ምስለኔዎች ለተባሉት ለምክትሎቻቸው፤ ከአዲስ አበባ የወጣውን አዋጅ ሕዝቡን እየሰበሰባችሁ አስረዱ እያሉ ትዕዛዝ ከማስተላለፍ በስተቀር ከሕዝቡ ጋር ቀጥታ የሆነ ምንም ዓይነት ግንኙነት አያደርጉም። እነዚህም "ምስለኔ" የተባሉት ኃላፊነቱ የወደቀባቸው ሰዎች፤ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት በየጊዜው የሚወስደውን እርምጃ እንኳንስ ለሕዝቡ ለማስረዳት፤ ራሳቸውም በትክክል የተረዱ አይደሉም። እንግዲህ ! ልዑል ጌታዬ እንደሚያዩት ከሕዝቡ ጋር ቀጥታ የሆነ የዕለት ግንኙነት ያላቸው ምስለኔዎች መሆናቸው

ከተረጋገጠ፤ እነሱን ማስተማርና ማሻሻል ለጠቅላይ ገዥዎች ከፍ ያለ እርዳታ ይሰጣል ማለት ነው።

**ራስ ካሣ** አሁን ከተናገርከው እንደተረዳሁት፤ መንግሥት ለሕዘብ አስተዳደር ማሻሻያ የሚያስበውን ሁሉ አንተ እንደምትለው ለተራው ሕዝብ ለማስረዳት፤ በመጀመሪያ ጉዳዩን በትክክል ማወቅና መረዳት አስፈላጊ ከሆነ፤ እንግዲያውስ ! የመንግሥትን ሐሳብ መማርና ማወቅ ያለባቸው ገዥዎቹ ናቸው እንጂ፤ እነሱ ተዘንግተው ዝቅ ላሉት ጭፍሮቻቸው ቅድሚያውን መስጠት ለምን አስፈለገ ? .....

**መኰንን ሀ.ወ** ቀደም ብዬ ለጌታዬ እንደገለጽኩት፤ ጸሐፊ ትዕዛዝ በአገር ግዛት ሚኒስትርነቱ እኔም በእርሻ ኃላፊነቴ በቅን መንፈስ ተነሳሥተን የጀመርነው፤ ምስለኔዎቹንና ጭቃ ሹሞቹን በማሠልጠን አገረ ገዥዎች ላይ የወደቀውን ከባድ ኃላፊነት ለማቃለል ይረዳል ብለን ነው። ልዑል ጌታዬ እንደሚያውቁት፤ ጭፍራ ችሎታ ሲኖረውና ብልህ ሆኖ ሲገኝ፤ ከበላይ የሚላከለትን መምሪያ በሚገባ በመፈጸም የሚያረካ አገልግሎት ሊያበረክት ይችላል። እኛም ይህንን ስብሰባ ያዘጋጀነውና ያካሄድነው ይህንን ግብ ለማግኘት ነው።

**ራስ ካሣ** መቸም ይህንን የምትለውን ሁሉ ከአገረ ገዥዎቹ ጋር ተመካክራችሁ አብራችሁ የምትሠሩት ቢሆን ኖሮ ባልከፋ ነበር። ነገር ግን የእናንተ አሠራር በዚህ አኳኋን አለመሆኑ የታወቀ ነው። አንተና ጸሐፊ ትዕዛዝ መጀመሪያ ሐሳቡን ስትወጥኑ፤ ቀጥሎም ጃንሆይን አስፈቅዳችሁ የምትፈልጉትን ስትሠሩ፤ አገረ ገዥዎቹን ከጉዳዩ ውጭ አድርጋችኋቸዋል። ይኸንን መካድ አትችሉም። በእኛ አመለካከት ለአገርና ለሕዝብ መሻሻል አሠራሩ በዚህ እናንተ በተከተላችሁት መንገድ አይደለም። መቸም በእናንተ አስተያየት፤ በአገራችን የፈረንጆቹን ሥልጣኔ ለማስፋፋት እንዳይቻል ዋናዎቹ ዕንቅፋቶች አገረ ገዥዎቹ ናቸው ብላችሁ ወስናችኋል። አሠራራችሁም የሚያሳየው ይኸንኑ መንፈስ መሆኑን መደበቅ አይገባም። በዚህ ምክንያት እናንተ አገረ ገዥዎቹን አትወዷቸውም። እነሱም ሐሳባችሁን በቅን መንፈስ አይመለከቱትም። አሁን በመጨረሻ የሠራችሁትን ስናጠናው ሐሳባችሁ ግልጽ ነው። የእናንተ ሐሳብ፤ በየአውራጃው ያሉትን መስለኔዎችንና ጭቃሹሞችን እያስተማርን፤ ሕዝቡንና መንግሥቱን እያቀራረብን፤ አሁን ያሉትን ገዥዎች ከኃላፊነታቸው ለማግለል ይመቸናል የሚል መሆኑን ሰምተናል። በእኛ በኩል ይኸ ሐሳባችሁ መቸውንም እንደማይሰምር ብታውቁት ይሻላችኋል። የኢትዮጵያ ሕዝብ ብዙ ታሪክ፤ ብዙ ባህልና ወግ አለው። የፈረንጅ ፊደል የቆጠረ ሁሉ፤ ከየሜዳው ተነሥቶ ልግዛህ ቢለው አይቀበልም። አንድ ሰው የሕዝብ ገዥ እንዲሆን ከንጉሥ ተመርጦ የሚሾመው፤ ከድሃ ወገን የተወለደው ብቻ ነው ተብሎ የወጣ ደንብ የለም። ...... በዚያ በመከራው የስደት ዘመን፤ እጅግ ሠለጠነ በተባለው በእንግሊዝ አገር እንዳየነው፤ ጌታም በጌትነቱ፣ ድሃም በድህነቱ በሰላም ሠርቶ የሚኖር ነው። መንግሥት የሚያስበው ለሁሉም ወገን እኩል ዳኝነት እንዲኖር ዋስትና መስጠትን እንጂ፤

በትውልዱ ምክንያት አንዱን ከአንዱ በሥልጣን ማበላለጥ አይደለም። በነገሥታቱም ዘንድ፣ ለመሳፍንቱና ለመኳንንቱ ትክክለኛው የተከበረው ቦታው አልተነፈገውም። በአገራችን ግን እናንተ የምትጠሉት መሳፍንትና መኳንንት፣ ከዚህ ቀደም ለአገር ነፃነት መሥዋዕት እየሆኑ፣ ብዙ የሚያኮራ ታሪክ የፈጸመና የአገርን ትልቅነት አስከብሮ የኖረ መሆኑን መርሳት አይገባም። ባለንበትም ሰዓት አብዛኛዎቹ ጠቅላይ ገዥዎች ሆነው የተመረጡት፣ ከጨዋው ቤተሰብ የመጡና አስተዳደርንና ዳኝነትን ደህና አድርገው የሚያውቁ ስለሆኑ፣ እነሱ ለአገር ጥቅም የሚሰጡትን አገልግሎት ማቃለል አይቻልም። ይኸንን ደህና አድርጋችሁ ብታጠኑት፣ በአሁኑ ጊዜ እነዚህን የመሳሰሉ ታላላቅ ሰዎች እያሉ፣ ለሕዝቡ መልካም አስተዳደር ከምስለኔዎችና ከጭቃ ሹሞች መካከል መርጦ ማዘጋጀት ይቻላል የምትሉት፣ እናንተ ብቻችሁን መሆናችሁን ማወቅ ትችሉ ነበር።

በእንተና በጸሐፊ ትዕዛዝ መካከል መግባባትና መተባበር ሊኖር የቻለው፣ ጃንሆይ በሁለታችሁም ላይ ሙሉ ዕምነት ስለአሳደሩባችሁና የምትፈልጉትን ሁሉ መሥራት እንድትችሉ፣ ዕድሉን ስለሰጧችሁ ነው። ታዲያ ፤ ይህን የተጣለባችሁን ዕምነት በሥራ የምትገልጹት፣ የጌታ ልጅ፣ የድሃ ልጅ በማለት ሕዝቡን እየከፋፈላችሁ፣ ወገኖቻችሁን ለመጥቀምና ሲያስፈልጋችሁም በእነሱ ለመጠቀም የምትዘጋጁ መስላችሁ እንዳትገኙ፣ ብርቱ ጥንቃቄ ብታደርጉበት ማለፊያ ይሆናል። እኔ ሁለታችሁንም ለማነጋገር የፈለግኩት ይህንኑ ለመንገር ስለሆነ፣ ከዚህ ሌላ የምጨምረው አለመኖሩን ለጸሐፊ ትዕዛዝም አንተ አስረዳው ..... "

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ ልዑል ራስ ካሣ የሚያስቡትን ሁሉ ደህና አድርገው ከገለጹ በኋላ፣ አቶ መኰንን መልስ እንዲሰጡበት ጊዜ አልሰጧቸውም። " ..... በል ደህና ዋል ..... " ብለዋቸው ወደ ጃንሆይ ቢሮ ሄዱ። በመሠረቱ የእርሻ ሚኒስትሩ ከመስፍኑ ጋር በክርክር መጋተሩ አደጋ እንደሚያስከትል ስለተረዱት፣ በመጨረሻ ለገለጹት ከባድ አስተያየት፣ መልስ እንድሰጥ ይፍቀዱልኝ ብለው አጠንክረው አልጠየቁም። ራስ ካሣ የተናገሩት ራሳቸው የሚያምኑበትን ብቻ ሳይሆን፣ ከነ ወልደጊዮርጊስ ተቃዋሚዎች የሰሙትን ጭምር ስለሆነ፣ ጃንሆይ የጠየቁ እንደሆነ ለማስረዳት፣ አቶ መኰንን ማስታወሻቸውን በዝርዝር አዘጋጅተው ተጠባብቀው ነበር። ነገር ግን፣ ንጉሠ ነገሥቱ ምንም እንኳ በዚህ በምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች ጉባኤ ምክንያት ከየጠቅላይ ገዥዎቹ ከፍ ያለ ተቃውሞ መገለጹን ደህና አድርገው ቢያውቁም፣ በወልደጊዮርጊስና በመኰንን ሀብተወልድ ላይ ምንም ዓይነት የቅሬታ መንፈስ አላሳዩም። ጠቅላይ ገዥዎቹም እጅግ ከማዘናቸው የተነሣ፣ የአገር ግዛትና የእርሻ ሚኒስትሮቹ ንጉሠ ነገሥታችንን አሳስተው ከደንቡ ውጭ በፈጸሙት ሥራ ከሹመታቸው ሊሻሩ ይገባል የሚል አቤቱታ ለማቅረብ በመዘጋጀት ላይ ናቸው ተብሎ ተወርቶ ነበር። ይሁን እንጂ፣ በመጨረሻ እንደታየው መሳፍንትና መኳንንት የሆኑት ገዥዎች በደረሰው ሁኔታ ምንም እንኳ ብርቱ ብስጭት ቢያድርባቸውም፣ ሚኒስትሮቹን ይሻሩልን በማለት ጃንሆይን ለማስቸገር አልሞከሩም። ወልደጊዮርጊስና መኰንንም ያቀዱት ፕላን ምን ጣጣ እንደሚያስከትል በጥልቀት ሳያጠኑና አዋቂዎች ሳያማክሩ ስሕተት ላይ ወድቀው መታየታቸውን ንጉሠ ነገሥቱ አልጠሉትም እየተባለ በቤተመንግሥቱ አካባቢ

ሲነገር ተሰምቷል። ምክንያቱም፤ ሁለቱ የንጉሥ ባለሟሎች፤ ለአገሩና ለሕዝቡ ዕድገት መንግሥት መሥራት የሚገባውን ሁሉ ጥቅምና ጉዳቱን ለይተን የምናውቀው እኛ ብቻ ነን በማለት፤ በራሳቸው ላይ ከፍ ያለ ዕምነት አሳድረው ስለነበረ፤ የዚህ የምስለኔዎቹ ጉባኤ ጉዳይ ደጋፊ አሳጥቶ ብቻቸውን ስለአስቀራቸው፤ ከእንግዲህ ወዲህ በማናቸውም የመንግሥት ጉዳይ እኛ ያልነው ብቻ ትክክል ነው እያሉ የሚያስቸግሩትን ማቆም ይችላሉ የሚል ተስፋ በማሳደር ነው ይባላል።

እንግዲህ ! ከዚህ በላይ በዝርዝር እንደቀረበው፤ በምስለኔዎቹ ጉባኤ ጉዳይ በአገር ግዛትና በእርሻ ሚኒስትሮቹ ላይ በየጠቅላይ ግዛቱ ከፍ ያለ የተቃውሞ እንቅስቃሴ ቢደረግም፤ በንጉሠ ነገሥቱ ዘንድ የሁለቱ ባለሟሎች ሥልጣን ከነበረበት አልተለወጠም። ሆኖም፤ ወልደጊዮርጊስና መኰንን ሀብተወልድ በአደባባይ ገልጠው ባይናገሩትም የደረሰውን ስሕተት የተገነዘቡት ስለሆነ፤ ለወደፊቱ ብርቱ ጥንቃቄ በማድረግ አንድነታቸውን እያጠነከሩ የሥልጣን ጉዞአቸውን ቀጥለዋል። መቆሚያቸው የትላይና መቼ እንደሚሆን በዚያን ጊዜ አልታወቀም።

# ምዕራፍ ፳

## " ዓረብ-ቤት" የሚባለውን የመንደር ገበያ መለወጥ

ጠላት ድል ሆኖ የኢትዮጵያ ነፃነት ከተመለሰ በኋላ፤ በአዲስ አበባና በየጠቅላይ ግዛቱ ባሉት ዋና ዋና ከተሞች ከየመን እየፈለሱ ወደ ኢትዮጵያ የገቡት ዓረቦች፤ ኪዎስኮች በብዛት እያቋቋሙ ለየሠፈሩ ነዋሪ ሕዝብ የሸቀጣ ሸቀጥ ችርቻሮ ንግዳቸውን አስፋፍተው ይኖሩ ነበር። ኢትዮጵያውያኖቹም ይህን በየሠፈራቸው የተመሠረተውን ንግድ "የዓረብ ቤት" እያሉ በመጥራት ለዕለት ኑሮ የሚያስፈልጓቸውን ዘይትና ስኳር፣ ጨውና ቅመማ ቅመም፣ ሻይና ቡና፣ ክብሪትና ሻማ፣ የፋኖስና የኩራዝ ማብሪያ የሆነውን ነጭ ጋዝና ላምባ፣ ዕጣንና ብርጉድ፣ ..... የመሳሰሉትን ስለሚገዙ፤ የዓረቦቹ ንግድ እጅግ እየተስፋፋ ሄደ።

ይህን የመሰለው የንግድ ሥራ ኢትዮጵያኖቹን በገዛ አገራቸው እጅግ የሚጐዳቸው መሆኑን የተገነዘቡት አቶ መኰንን ሀብተወልድ፤ እሳቸው በሚመሩት በንግድ ሚኒስቴር ውስጥ ሰፊ ጥናት ተደርጐ፤ አንድ መፍትሔ እንዲገኝለት ልዩ ኰሚቴ አቋቋሙ። የአቶ መኰንን ሀብተወልድ ጭንቀትና ሥጋት፤ የውጭ ዜጐች የሆኑት ዓረቦች፤ የኢትዮጵያውያኖች ቀጥታ መብት የሆነውን የየመንደሩን የችርቻሮ ንግድ በሙሉ ይዘው ከበርቴ መሆናቸው ብቻ ሳይሆን፤ ዓረቦቹ በሚኖሩባቸው ቀበሌዎች ወጣት ሴት ልጆችን በገንዘብ እያደለሉ እንደ ሚስት በመያዝ ብዙ ልጆች ካስወለዱ በኋላ፤ በመጨረሻው ለወለዷቸው ልጆች አንዳች የመኖሪያ ገንዘብ ሆነ የመቋቋሚያ ንብረት ሳያዘጋጁላቸው፤ ያከማቹትን ጥሬ ገንዘብ ይዘው የንግዳቸውን ድርጅት ለወገናቸው አስተላልፈው ወደ አገራቸው መመለሳቸው ነው። እነዚህ ቁጥራቸው በርካታ የሆኑት ከዓረቦቹ ራስ በራስ የተወለዱት ሕፃናት፤ አባቶቻቸው ባዶ ሜዳ ላይ ጥለዋቸው ሲሄዱ፤ በየተወለዱበት ሠፈር ሲንገላቱና ሲቸገሩ ማየት እጅግ የሚያሳዝን ነበር። እነዚህን የዓረቦች ልጆች ማን ያኑራቸው ? ማንስ ያሳድጋቸው ? ..... እናቶቻቸውም በየሠፈሩ እነዚህ የዓረብ ሚስቶች እየተባሉ፤ እንኳንስ ለትዳር የሚፈልጋቸው፤ ለሠራተኛነትም የሚቀጥራቸው ማግኘት አልቻሉም።

የንግድ ሚኒስቴር ዋና ዋና ኃላፊዎችና የኢትዮጵያ ሕዝብ ያገር ፍቅር ማህበር አባሎች የተገኙበት ኰሚቴ ጥናቱን አካሂዶ ባቀረበው ሐሳብ፤ " ... ምንም እንኳ የየመን ዓረብ ተወላጆች ወደ ኢትዮጵያ እየመጡ የሸቀጣ ሸቀጦች የንግድ ሥራ የጀመሩት ከጠላት በፊት ቢሆንም፤ ዛሬ በየከተማው ሱቆች በብዛት እያቋቋሙ የየሠፈሩን የችርቻሮ ንግድ አስፋፍተው የያዙት፤ በፋሽስት አስተዳደር ዘመን በገፍ በተሰጣቸው የንግድ ሥራ ፈቃድ ነው። ስለዚህ፤ በአሁኑ ሰዓት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ መንግሥት አዲስ አዋጅ በማውጣት፤ ከእንግዲህ ወዲህ በየሠፈሩ የሚካሄደው "ዓረብ ቤት" እየተባለ የሚጠራው የችርቻሮ የንግድ ፈቃድ ለውጭ አገር ተወላጆች የተከለከለ መሆኑን ማስታወቅ የመጀመሪያው እርምጃ ይሆናል። በዚሁ አዋጅ ላይ በተጨማሪ ማብራራት የሚያስፈልገውም፤ ወደፊት አዲስ የችርቻሮ የንግድ ፈቃድ ለውጭ አገር ተወላጆች በሙሉ የተከለከለ መሆኑ

ሲገለጽ፣ እስከ ዛሬ ድረስ ፈቃዱ ተሰጥቷቸው ንግዳቸውን ሲያካሂዱ የቆዩት የውጭ አገር ተወላጆች፣ የያዙት ፈቃድ ጊዜው እስከሚያልቅ ድረስ፣ ሥራቸውን ለመቀጠል እንደሚችሉ ማስታወቅ ይጠቅማል የሚል ነበር።

የንግድ ሚኒስትሩ በዚህ ከኮሚቴው በቀረበላቸው ሐሳብ ውስጥ፣ ወደፊት በየሠፈሩ ለሚካሄደው የችርቻሮ ንግድ ሥራ ለውጭ አገር ዜጐች መከልከሉን አዋጅ ማውጣት አስፈላጊ ነው ብለው ቢያምኑበትም፣ የችግሩ የመጨረሻው መፍትሔ አለመሆኑን በማየት፣ ዓረቦቹ እስከዛሬ የያዙትን ሥራ ኢትዮጵያውያኖች ወዲያውኑ እንዲረከቡ ለማድረግ ዘዴው ምን እንደሆነ ኮሚቴው ጥናቱን እንዲቀጥል ጠየቁ።

በዚህ ውሳኔ መሠረት፣ የንግድ ሚኒስቴርና የአገር ፍቅር ማህበር አባሎች ተሰብስበው ጥናታቸውን በሚያካሂዱበት ጊዜ፣ ለዚህ ኮሚቴ ቃለ ጉባኤ ያዥና ላይዘን ኦፊሰር ሆኖ እንዲሠራ መኰንን ሀብተወልድ የመረጡት፣ "ሩጋ አሻሜ" የተባለ ዕድሜው ሠላሳኛውን ዓመት ያልሞላ ወጣት፣ አንድ ሐሳብ ተገለጠለት። ይኸውም፣ ለወጣቱ ሩጋ የታየው በዚህ የሠፈር ችርቻሮ ንግድ ዓረቦቹን ተቋቁመው የተያዙትን ቦታዎች ማስለቀቅ የሚችሉት የትውልድ አገሬ ተወላጆች "ጉራጌዎች" ብቻ ናቸው የሚል ነበር። ይህንንም ሐሳቡን በቀጥታ ለኮሚቴው ያቀረበ እንደሆነ፣ ወጣቱ ሩጋ እሱ ራሱ ጉራጌ በመሆኑ ነው ብለው አባሎቹ ሊያፌዙብኝ ይችሉ ይሆናል የሚል ሥጋት ስለአደረበት፣ በቅድሚያ የንግድ የኢንዱስትሪና የእርሻ ሚኒስትር ለሆኑት ለመኰንን ሀብተወልድ በአንድ ብርቱ ምሥጢር በሚል ማስታወሻ ሐሳቡን ገለጸ። " .... ጌታዬ የተጨነቁበትን ጉዳይ፣ እኔም በአቅሜ ካለፉት አምስት ዓመታት ወዲህ ያለማቋረጥ ሳስብበት ቆይቻለሁ። ለችግሩ መድኃኒቱ ተፈልጐ በአስቸኳይ እንዲቀርብልዎ፣ ጌታዬ መምሪያዎንና አደራዎን ለኮሚቴው ሲሰጡ፣ ኃላፊነቱ የሁላችንም ነው። .... በእኔ በትንሹ ሠራተኛዎ አስተያየት በገዛ አገራችን በችርቻሮ ንግድ የወረሩንን እነዚህን ዓረቦች ማስለቀቅና ማስናበት የምንችለው፣ ከኢትዮጵያ ሕዝቦች መካከል ለጊዜው ቁጥራቸው አምሳ የሚሆኑትን ወጣት ጉራጌዎች መርጠን፣ ዓረቦቹ በከፈቷቸው ሱቆች አጠገብ ተመሳሳይ ሱቅ እየከፈቱ፣ ነዋሪውን ሕዝብ በኢትዮጵያዊነት መንፈስና በዋጋ ቅናሽ እየማረኩ በርትተው ሲሠሩ ነው። ዓረቦቹ በዚህ አኳኋን የመጣባቸውን ውድድር ተቋቁመው ለማሸነፍ ስለማይችሉ፣ ሱቆቻቸውን እየዘጉ በሰላም ወደየአገራቸው ከመመለስ በስተቀር ሌላ ምርጫ አይኖራቸውም። ትግላችንን በዚህ ሁኔታ እንድንቀጥል ክቡርነትዎ የሚስማማበት ከሆነ፣ ለሥራው የሚመረጡት አምሳዎቹ ወጣት ጉራጌዎች በየተወለዱበት ቀበሌ በሚገኙት ያገር ታዋቂ ሽማግሌዎች የታመኑና ዋስትና የሚሰጣቸው ስለሚሆኑ፣ ለንግዳቸው ማቋቋሚያ ወጭው ተተምኖ በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ ተከፍሎ የሚጠናቀቅ ብድር መንግሥት ሊሰጣቸው የሚገባ ይሆናል። ..... በእኔ በትንሹ ሠራተኛዎ ዕምነት የክቡርነትዎ የሌሊትና የቀን ጭንቅ መድኃኒት ሊያገኝ የሚችለው፣ በዚህ ባቀረብኩት ኘላን የሚሆን ስለመሰለኝ፣ ሐሳቡ በክቡርነትዎ በኩል ለኮሚቴው ቀርቦ ዝርዝር ጥናት እንዲደረግበት አሳስባለሁ። እኔን ትንሹን ሠራተኛዎን፣ የኮሚቴው ቃለ ጉባኤ ያዥና ከክቡርነትዎ ጽሕፈት ቤት ጋር ላይዘን ኦፊሰር አድርገው በሰጡኝ ሹመት፣ ይህንን ሐሳቤን ለአባሎቹ አቅርቤ መከራከሩ ባልቸገረኝ ነበር። ነገር ግን ጌታዬ እንደሚያውቁት የዓረቦቹን ነጋዴነት ተወዳድረው የሚያሸንፉት ጉራጌዎች ስለሆኑ፣ ኃላፊነቱ ለእነሱ ቢሰጥ ይሻላል ብዬ ስናገር፣ "ሩጋ አሻሜ ተሸምቶ ለተወላጆቹ አደላ" ብለው እንዳያፌዙብኝ በማሰብ ነው። ......

ከክቡር ጌታዬ አጠገብ የመሥራት ዕድል ካጋጠመኝ ጊዜ ጀምሮ አንድ ትልቅ ነገር ተምሬአለሁ። ይኸውም፣ እያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ በተግባሩ ለኢትዮጵያና ለሕዝቦቿ አንድነት መጣር የመጀመሪያ ግዳጁ መሆኑን ነው። በዚህም መሠረት አገራችን የምትለማውና የምታድገውም፣ በየአውራጃው ያለው ኢትዮጵያዊ በየሞያውና በየዝንባሌው ተግቶ ሲሠራ ነው ብዬ አምናለሁ። ለምሳሌም፣ ከዓረብ ነጋዴዎች ጋር ለሚያስፈልገው ውድድር ተወላጆቹ ጉራጌዎች የተሻሉ ይሆናሉ ብዬ ስናገር፣ ሞያቸውንና ችሎታቸውን በመመርኮዝ እንጂ፣ በተለይ ወገኖቼን ለመጥቀም በተመሠረተ ሐሳብ ላይ አለመሆኑን ጌታዬ እንደሚገነዘቡልኝ ዕምነቴ ሙሉ ነው። ጌታዬ፣ እንደ አለቃ እንደ መሪ ሳይሆን እንደ አባት ሆነው በየጊዜው በሚሰጡኝ ትምህርትና ማበረታቻ ተደፋፍሬ የሚመስለኝን ሐሳብ አቅርቤያለሁ።

ፍጹም ታዛዥዎ ሩጋ አሻሜ

መኰንን ሀብተወልድ ወጣቱ ሩጋ ባቀረበላቸው ሐሳብ በጣም ተማረኩ። በማግሥቱ በአገር ፍቅር ማህበር ጽሕፈት ቤታቸው ኮሚቴውን ሰብስበው፣ የሩጋ አሻሜን ስም ሳያነሱ፣ ከአንድ ትጉህ ሠራተኛዬ የቀረበልኝ በሚል መነሻ፣ ሐሳቡን ተንትነው ለአባሎቹ ገለጹ። በመጨረሻም፣ " ..... እኔ በቀረበልኝ ሐሳብ ተስማምቼበታለሁ። እናንተ የአፈጻጸሙን ቅደም ተከተል በዝርዝር አጠንታችሁ በአንድ ሳምንት ውስጥ እንድታቀርቡልኝ .... " የሚል ውሳኔ ሰጥተው ስብሰባውን በተኑ። የኮሚቴው አባሎች በየፊናቸው ልዩ ልዩ ሐሳብ እየነደፉ ከመጨቃጨቅ፣ ሚኒስትሩ የተስማሙበትን ተከትለው የአፈጻጸሙን አሠራር ማዘጋጀት የቀለለ ሆነላቸው። ከአጥኚዎቹ መካከል አንዳንዶቹ፣ አዲስ የሚፈጠረውን የንግድ ሥራ ለጉራጌዎች ብቻ ከመደልደል፣ ለሌሎቹም ብሔሮች ለምሳሌ ለወሎዬዎችና ለትግሬዎች እንዲከፋፈል ቢታሰብበት ይሻል ይሆናል የሚል ሐሳብ የሰነዘሩ ነበሩ። ሚኒስትሩ ወዲያውኑ በሰጡት መልስ፣ " .... ይህን ሐሳብ የምንደግፈው ብቻ ሳይሆን ከልብ የምናምንበት ነው። እንደምታውቁት፣ ዓረቦቹ ንግዳቸውን ያስፋፉት በአዲስ አበባ ከተማ ብቻ ሳይሆን በሌሎቹም የአውራጃ ከተሞች ነው። አሁን እንዳላችሁት፣ ከወሎና ከትግሬ ወንድሞቻችን መካከል ዓረቦቹ ይዘው የሚጠቀሙብንን የንግድ ሥራ እየተወዳደርን እጃችን ለማስገባት እንችላለን ብለው ሲቀርቡልን፣ ዕድሉን የምንሰጣቸው በደስታ ነው። ለእነሱም ብቻ ሳይሆን ለሌሎቹም በሩ ክፍት ነው .... " አሉ።

በመጨረሻው፣ በወጣቱ በሩጋ አሻሜና በጓደኞቹ ጥረት ለመጀመሪያ ጊዜ ተመርጠው የቀረቡት ዐርባዎቹ የጉራጌ ነጋዴዎች፣ የሚያስፈልጋቸውን እርዳታ ተቀብለው በአዲስ አበባ ከተማ ሥራቸውን በአስቸኳይ እንዲጀምሩና በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ የሚሰጡት ውጤት ታይቶ ውሳኔ እንዲሰጥበት፣ የኮሚቴው አባሎች በሙሉ ከስምምነት ላይ ደረሱ። እነዚህም ዐርባዎቹ ወጣት ነጋዴዎች፣ በየሠፈሩ በሚገኘው ዓረብ ቤት አጠገብ፣ ሱቅ እያቋቋሙ ንግዳቸውን ለመጀመር ወደፊት በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ ከሚያገኙት ትርፍ የሚከፍሉት ለእያንዳንዳቸው ሰባት መቶ የኢትዮጵያ ብር (700.00) መንግሥት እንዲያበድራቸው ኮሚቴው የተስማማበትን፣ መኰንን ሀብተወልድ ለንጉሠ ነገሥቱ አቅርበው አስፈቀዱ። ይህ ሰባት መቶ የኢት. ብር የተተመነው፣

ሀ/ ለሱቁ መሥሪያ ሁለት መቶ ብር

ለ/ ለንግድ ዕቃዎች ማዘጋጃ አምስት መቶ ብር እንዲሆን ነበር።

ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ ሩጋ አሻሜ (ኋላ ፊታውራሪ) በዓረቦቹ የተያዙትን የሠፈር ንግዶች ተቋቁሞ ለማሸነፍ የተሻለ ዘዴ ይሆናል ብለው ያቀረቡትን ሐሳብ፣ የንግድ ሚኒስትሩ በይፋ እንዲታወቅላቸው ለማድረግ የወሰኑት፣ ጉዳዩን ከሚቴው አጥንቶ ከተስማማበት በኋላ እንዲሆን ነበር። በዚህ ጊዜ ሩጋ አሻሜ ለመኩንን ሀብተወልድ ባቀረቡት ልዩ ማስታወሻ የሚከተለውን ገለጹ። " .... እኔ ትንሹ ሠራተኛዎ ባለኝ ችሎታና አቅም በማሳየው የሥራ ጥረት፣ ከጓደኞቼና ከታላላቆቼ የተለየ አድናቆትም ሆነ ምስጋና እንዳገኝ ክቡርነትዎን ማስቸገር አልፈልግም። ይልቁንም ወደፊት የተደቀኑብኝ የኃላፊነት ሥራዎች ብዙዎች ስለሆኑ፣ ከጌታዬ የሚሰጡኝን አድናቆቶች ሆኑ ወይም ሽልማቶች ተቆጥበው እንዲቀመጡልኝ አጥብቄ እለምናለሁ። አሁንም፣ ጌታዬ በጣም የተጨነቁበት ንጉሠ ነገሥታችንም ከልባቸው ያሰቡበት፣ በየመንደሩ የተጥለቀለቁትን የዓረብ የንግድ ቤቶች ወደ ኢትዮጵያውያን እጅ ለማዛወር፣ ሥራው እንዲጀመር ተወስኗ እንጂ፣ ፍሬውን አላሳየም። ይሁን እንጂ፣ ሁላችንም ቃል እንደገባነው፣ ከዛሬው ዕለት ጀምሮ በዚህ በመጭው አንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ ቆርጠን የተነሣንበትን ለማሸነፍና ለማስፈጸም ስንችል፣ በተለይ እኔ ትንሹ ሠራተኛዎ ከጌታዬ የምጠብቀው ምስጋና ብቻ ሳይሆን ትልቅ ሽልማት ነው .... " አቶ መኩንን በሩጋ አሻሜ ላይ ከቀድሞው የበለጠ ከፍ ያለ አድናቆት አደረባቸው። የሩጋን ብልህነትና አርቆ አሳቢነትም ምን ያህል የጠለቀ መሆኑን ለጃንሆይ ነገሩላቸው።

እንደታሰበው፣ ጉራጌዎቹ ነጋዴዎች በየዓረቡ መደብር አጠገብ ሱቆቻቸውን እየተከሉ ንግዳቸውን ሲጀምሩ፣ የሠፈርተኛው ሕዝብ መልካም ትብብር ስላልተለያቸው፣ ያደረባቸው ትጋትና የጋለ ስሜት እጅግ የተለየ ሆኖ ይታይ ነበር። አንድ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ ከዐርባዎቹ ነጋዴዎች መካከል ሠላሳ ሦስቱ (33) በዓረቦቹ ተይዞ የነበረውን ንግድ በሙሉ ቀልብሰው ስለወሰዱት፣ የመኒቶቹ የነበራቸውን ሱቅ እያፈረሱ ከሠፈሩ መጥፋት ግዴታ ሆነባቸው። የየሠፈሩም ነዋሪ ሕዝብ ለዕለት ኑሮው የሚያስፈልገውን ሁሉ ለመገብየት በወገንና በውጭ ዜጋ ነጋዴዎች መካከል ያለውን ልዩነት ስለተረዳው፣ የዓረቦቹን መደብር እየተወ ግልብጥ ብሎ ወደ ኢትዮጵያውያኖቹ ሱቆች ለማምራት ጊዜ አልፈጀም። ኢትዮጵያውያኖቹም ነጋዴዎች የሠፈሩ ነዋሪ ሕዝብ ለዕለት ኑሮው የሚያስፈልጉትን ሁሉ ከየዓረብ ቤቱ በተሻለ አኳኋን አሟልተው መገኘታቸው ብቻ ሳይሆን መጠነኛ የሆነ የዋጋ ቅናሽ በማድረጋቸውም ተጠቃሚዎቹን ለመማረክ ችለዋል።

ከዚህ በላይ ደግሞ የንግድ ሚኒስትሩን እጅግ አድርጐ ያስደነቃቸው፣ ነጋዴዎቹ በነጭ ወረቀት ላይ እየፈረሙ፣ እያንዳንዳቸው ከመንግሥት የተበደሩትን ሰባት መቶ ብር የውሉ ዘመን ሲፈጸም ሲቃረብ፣ ንግድ ሚኒስቴር እየሄዱ ዕዳችንን በደረሰኝ ተቀበሉን እያሉ ማስቸገራቸው ነበር። ከላይ እንደተገለጸው፣ ነጋዴዎቹ ገንዘቡን የተቀበሉት በብድር ስም በነጭ ወረቀት ላይ እየፈረሙ ስለሆነ፣ አሁን ገንዘቡን ሲመልሱ እነሱ እንደጠየቁት በገንዘብ ሚኒስቴር ደረሰኝ "ከመንግሥት የተሰጠ ብድር" እየተባለ ካርኒ መቁረጡ በጣም የሚያስቸግር ሆነ። ለአሠራሩ የሚሻለው፣ ነጋዴዎቹ በነጭ ወረቀት ላይ የፈረሙት የዕዳ ሰነድ እየተመለሰላቸው ገንዘቡን ቢያስገቡ ነበር። ነገር ግን፣ ጉራጌዎቹ በገንዘብ ክሽ ክሽ የለም። እኛ ገንዘቡን ስንቀበል "ብድር ነው" ብለን መፈረም ብቻ ሳይሆን ተያዥም እየሰጠን ነው። ስለዚህ የተበደርነውን ስንመልስ፣ ካርኒ የተቆረጠበት የመንግሥት ደረሰኝ ካልተሰጠን፣ ገንዘቡን ገቢ አናደርግም አሉ።

በመሠረቱ፤ የዓረቦቹን ንግድ ለመወዳደር ለተመረጡት ለዐርባዎቹ ነጋዴዎች፤ ንጉሠ ነገሥቱ የፈቀዱት ሐያ ስምንት ሺህ ብር (40x700=28.000) በብድር ስም እንዲሰጣቸው አልነበረም። ነገር ግን፤ በነፃ የተሰጣቸው እርዳታ መሆኑን ነጋዴዎቹ ካወቁ፤ ምናልባት የኃላፊነት ስሜት ላያድርባቸውና ገንዘቡንም ተቆጣጣሪ የለብንም በማለት ለታሰበው ጉዳይ በትክክል ላያውሉት ይችላሉ የሚል ሥጋት ተፈጠረ። ስለዚህ፤ በብድር ስም በነጭ ወረቀት እየፈረሙ ገንዘቡን እንዲቀበሉና ትርፍ ካገኙበት ዕዳቸውን እንዲከፍሉ፤ ኪሣራ ላይ ከወደቁ ደግሞ በዕዳ እንዳይጠየቁ ሚኒስትሩ ፈቅደው ሥራው የተጀመረው በዚህ መልክ ነበር። አሁን ግን ከዐርባዎቹ ነጋዴዎች ውስጥ ሠላሳ ሦስቱ ትርፍ ሲያገኙ ገንዘቡን ለመመለስ መቅረባቸው የሚያስደስት ሲሆን፤ የገንዘብ ሚኒስቴር የገቢ ደረሰኝ ካርኒ ካልተቆረጠልን ማለታቸው ለአፈጻጸሙ አስቸጋሪ በመሆኑ፤ ሌላ ዘዴ መፈለግ ግዴታ ሆነ። ዘዴው ተፈልጎ ከመገኘቱ በፊት፤ ነጋዴዎቹ ቀድመው ለንግድ ሚኒስትሩ አንድ የተለየ ሐሳብ አቀረቡ። " ..... እኛ የሸቀጣ ሸቀጥ ችርቻሮ ነጋዴዎች፤ ለጀመርነው የንግድ ሥራ ማስፋፊያ እንዲሆን አንድ ማህበር አቋቁመናል። የማህበራችን ዋና ተግባር፤ መንግሥታችን ለእኛ በቀየሰልን መንገድና በሰጠን ከፍተኛ ድጋፍ እስካሁን ከፍተኛ ውጤት ስለአገኘንበት፤ ይህንኑ ዓላማ በመከተል በየአውራጃዎቹ ባሉት ዋና ዋና ከተሞች ንግዱን እያቋቋምን የውጭ ዜጐች ከሆኑት ነጋዴዎች ጋር ለመወዳደር እንድንችል አስፈላጊውን እርዳታ መስጠት ነው። ባለፈው ዓመት ለሥራችን መቋቋሚያ መንግሥታችን ያበደረንን ገንዘብ ገቢ ለማድረግ ተዘጋጅተን ስንቀርብ፤ የንግድ ሚኒስቴር ስለ ደረሰኝ አሰጣጥ ጥናት በማድረግ ላይ ስለአለሁ፤ ለጊዜው ገንዘቡን መቀበል አልችልም ብሎ መለሰን። ክቡርነትዎ እንደሚያውቀው ይህ የተበደርነው ገንዘብ ሳንሠራበት በየኪሣችን ቢቀመጥ አንዳች ትርፍ ሊሰጥ አይችልም። ስለዚህ፤ ያቋቋምነው የንግድ ማስፋፊያው ማህበራችን ይህንን እጃችን ላይ የሚገኘውን ገንዘብ በብድር ተቀብሎ እንዲሠራበትና ትርፍ ሲያገኝ ለመንግሥታችን ገቢ እንዲያደርግ እንዲፈቀድለት ክቡርነትዎን እንለምናለን ..... " የሚል ነበር።

መኰንን ሀብተወልድ ይህን ሐሳብ የተመለከቱት በከፍተኛ አድናቆት ነበር። በአቀራረቡም ስለተደሰቱ፤ ጉዳዩን ለማስፈጸም ጊዜ አልወሰዱም። ልዩ ጸሐፊያቸውን ጠርተው፤ " .... ይህ የቀረበልኝ ሐሳብ፤ የጉራጌዎችን ንቃትና ብልህነት ደህና አድርጐ የሚያመለክት ነው። የመሥሪያ ቤታችንን የአሠራር ድክመት ተገንዝበው፤ "እምቢ" የማይባል ጥያቄ አቅርበውልናል። በመሠረቱ እኛ የምንፈልገው እነሱ ብርታታቸውን ቀጥለው ዓረቦቹን እንዲያባርሩልን ነው። እስካሁን ያስገኙት ውጤት በጣም ጥሩ ስለሆነ፤ አሁን የጠየቁትን በአቃቤ ሰዓት ለጃንሆይ አቅርቤ እንዳስፈቅድላቸው ማስታወሻው ይዘጋጅልኝ .... " ብለው ወሰኑ። ሚኒስትሩ ከልባቸው ስለአሰቡበት አንድ ሳምንት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ የንጉሠ ነገሥቱን መልካም ፈቃድ አግኝተው የጉራጌዎቹ ማህበር ገንዘቡን ተቀብሎ "የዓረብ ቤት" በሚል መጠሪያ በየከተማው የተጥለቀለቀውን ንግድ ቤት በውድድር እያዘጋ፤ የኢትዮጵያውያኖቹን መብት እንዲያስከብር ሙሉ ዕምነታቸውን ጣሉበት። በዚህ አኳኋን ጉራጌዎቹ ተጠናክረው ባሳዩት ብርቱ ጥረት፤ የየመን ዓረቦች አብዛኞዎቹ ሱቆቻቸውን እየዘጉ ወደየአገራቸው ሲመለሱ፤ ጥቂቶቹ ደግሞ ሌላ ባላንጣ ደርሶ እስከሚያባርራቸው፤ ወደ ዋናው ገበያ ወደ መርካቶ እየተዛወሩ፤ በልዩ ልዩ የጨርቃ ጨርቅ ንግድ ለመቋቋም ሞክረው ነበር። ሙከራቸው ብዙ ሊያቆያቸው ስላልቻለ፤ እነሱም ቀስ በቀስ እየመነመኑ ጠፉ።



" ... ይኸ ወጣት ሩጋ አሻሜ ያጠናውን ለጃንሆይ አቅርቤላቸው በሐሳቡ ስለተደሰቱ፤ እንዲፈጸም አዘዋል። አቶ ሩጋ ሥራውን እንደጨረሰ ግርማዊነታቸው ዘንድ ይቀርባል ... "

መ.ሀ.ወ

መኰንን ሀብተወልድ
የእርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር

" ... በገዛ አገራችን በችርቻሮ ንግድ የወረሩንን አረቦች ማስለቀቅ የምንችለው፤ ለጊዜው ሃምሳ የሚሆኑ ጉራጌዎችን መርጠን፤ አረቦቹ በከፈቷቸው ሱቆች አጠገብ ተመሳሳይ ሱቅ እያቋቋሙ፤ በኢትዮጵያዊነት መንፈስ የዋጋ ቅናሽ በማድረግ ተጠቃሚውን ሕዝብ ሲማርኩት ነው። ይህ ከሆነ፤ አረቦቹ ውድድሩን ስለማይችሉት ዘግተው ወደየአገራቸው ከመመለስ በስተቀር ሌላ ምርጫ አይኖራቸውም ... "

(ሩጋ አሻሜ)



አቶ ሩጋ አሻሜ (ኋላ ፊታውራሪ)
የመኰንን ሀብተወልድ ልዩ ረዳት

በዚያን ዘመን የዓረቦቹን ንግድ ለኢትዮጵያውያኖች ለማዛወር በተደረገው ጥረት የመኰንን ሀብተወልድ የቅርብ ረዳት ሆነው ከፍተኛ ተግባር በመፈጸም የተደነቁትን ፊታውራሪ ሩጋ አሻሜን፤ ከዛሬ አሥራ አምስት ዓመታት በፊት አዲስ አበባ በመጣሁ ጊዜ ፈልጌ አነጋግሬአቸው ነበር። ፊታውራሪ ሩጋ አሻሜ ለዚህ ሁሉ መልካም ሥራ አፈጻጸም፤ የምስጋናው ባለቤት አቶ መኰንን ሀብተወልድ መሆናቸውን በሰፊው ከማስረዳት በስተቀር በበኩላቸው ምን ያህል እንደደከሙና ምን ያህል እንደሠሩ መናገር አልፈለጉም። " ... እኔ የሠራሁት ሁሉ፤ መኰንን ሀብተወልድ የሰጡኝን መመሪያና የጣሉብኝን ዕምነት ተመርኩዤ ስለሆነ፤ ሌላ የምጨመረው የለም .... " በሚል ቃል ብቻ አስተያየታቸውን ደመደሙ።

በዚህ ምዕራፍ ላይ በየመልኩ ተዘርዝሮ እንደተገለጸው፤ ዓረቦቹ ከኢትዮጵያውያን ወጣት ነጋዴዎች ጋር መወዳደሩ እያቃታቸው ሱቆቻቸውን እየዘጉና ዕቃዎቻቸውን እየጠቀለሉ በሚሄዱበት ጊዜ፤ በየመኪቶቹ ላይ የሚታየው ብስጭት ቀላል አልነበረም። ነገር ግን፤ ጉራጌዎቹ የነገ ጥቅማቸውን በጥልቅ በመገንዘብ፤ ዓረብ ሲጨፍርባቸውና ሲዳንትባቸው፤ ከቁም ነገር ሳይቆጥሩ ያሳዩት ትዕግሥት፤ እጅግ የሚደነቅላቸው ብቻ ሳይሆን፤ የሚያስመሰግናቸውም ነበር። የሠፈሩ ነዋሪዎች ዓረቦቹ የሚያሳዩት ንዴትና ቁጣ ለምንድን ነው ? ብለው ለጠቡ ሲዘጋጁ፤ ጉራጌዎቹ "ግዴለም ትዕግሥት ከኛ ጋር ትሁን" ከእነሱ ጋር መጣላት የአገራችንን ክብር መቀነስ ነው እያሉ፤ የገላጋይ ሚና ሲጫወቱ ይታዩ ነበር። የንጉሠ ነገሥቱም መንግሥት ምንም ዓይነት የኃይል ሆነ የሕግ እርምጃ መውሰድ ሳያስፈልገው፤ "ዕድሜ ለጉራጌዎች" ችግሩን በዘዴና በሰላም ለመገላገል በመቻሉ ትልቅ ደስታ ሆነለት።

# ምዕራፍ ፤

# የጃንሆይን መንግሥት ለማሻሻል የሁለቱ ሰዎች ፕላንና አቋም

እንደ ኢት. አቆ. መጋቢት 11 ቀን 1939 ዓ.ም ከእኩለ ቀን በፊት በአራት ሰዓት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አምሳለ ገነት በተባለው ጽሕፈት ቤታቸው፤ ቢትወደድ መኮንን እንዳልካቸው ጠቅላይ ሚኒስትርን፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትርን፣ አቶ መኮንን ሀብተወልድ የእርሻ፣ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትርን አስጠርተው የሚከተለውን መምሪያ ሰጡ።

" ..... የውጭ መንግሥታቶችና የየሀገራቸው ጋዜጦች ስለ ኢትዮጵያ በየጊዜው የሚገልጹትን አስተያየት ስንመለከተው፤ የመንግሥታችን አስተዳደር የፊዎዳሎቹን አሠራር የሚከተል በመሆኑ፤ ኢትዮጵያ ዘመናዊውን ሥልጣኔ መቀበል አቅቷታል የሚል ወቀሳ ነው። ሁላችሁም እንደምታውቁት፣ ጠላት ከአገራችን ከተባረረና እንግሊዞችም የያዙብንን ሥልጣን በዘዴና በትዕግሥት ለማላቀቅ ከቻልን በኋላ፤ ለሥልጣኔ ዕድገታችን መሠረቱ ትምህርት ነው በማለት ጥረታችን ወሰን በሌለው መንገድ እንደቀጠለ ነው። ነገር ግን ያለብንን ችግርና ያለንንም የኤኮኖሚ አቅም በትክክለኛ ሚዛን ባለመመልከት የታላላቆቹ መንግሥታትና ጋዜጦቻቸው የሚነዙብን የነቀፋ ፕሮፓጋንዳ እጅግ የሚያሳዝን ሆኗል። ልጆቻችንን በፈረንጆቹ ደረጃ ለማስተማርና የሀገራችንን ኃላፊነት ለመቀበል ብቁ እንዲሆኑልን ያለማቋረጥ በየዕለቱ የምናደርገውን ድካም ታላላቆቹ መንግሥታት ተረድተው፤ ለግባችን የሚያስፈልገንን እርዳታ በቅን መንፈስ ቢለግሱን ኖሮ፤ ያለ ጥርጥር ውጤታችን የተፋጠነ በሆነ ነበር። መቸም እንደሚታወቀው የተማሩትን ሰዎች በብዛት አግኝቶ በዕውቀታቸው አገሪቱ እንድትጠቀም ማድረግ የሚቻለው፤ ጊዜ ወስዶ በማስተማር እንጂ፤ ለሽያጭ እንደተዘጋጀ ዕቃ ከያለበት በገንዘብ ተገዝቶ በሥራ ላይ የሚውል አይደለም። በተጨማሪም ማስተማሩ ብቻ በቂ አይደለም። ከብዙ ዓመታት ትምህርት በኋላ ደግሞ ለአገሪቱ በአስቸኳይ ጠቃሚ የሚሆኑት ጉዳዮች ምንና ምን መሆናቸውን አጥንቶ በሥራ እንዲገለጹ ለማድረግ ጊዜ የሚጠይቅ ነው። ታላላቆቹ መንግሥታት ይህን ሁሉ ሳይገነዘቡት ይቀራሉ ብለን አናስብም። ይሁን እንጂ፤ በየጊዜው በተለይ ትምህርትን በሚመለከተው ጉዳይ የምንጠይቃቸውን እርዳታ እየነፈጉን፤ የኢትዮጵያ አስተዳደር ከጨለማው ዘመን አልወጣም። በጥንታዊው የፊውዳል አመራር ላይ የሚገኝ ነው እያሉ የሚያወርዱብን ስድብ፤ ምን ጥቅም ለማግኘት እንደሆነ ሊገባን አልቻለም። የሆነ ሆኖ የምንወቀስበትን ጉዳይ ሁሉ በቁም ነገር ማጥናት እንጂ በቸልታ ማለፍ አይገባንም። ዛሬ እናንተን የቅርብ ታማኞቻችንን የጠራናችሁም በዚህ ጉዳይ ላይ ጥናት አድርጋችሁ በተፋጠነ መንገድ አንድ ሐሳብ እንድታቀርቡልን ነው። መቸም እንደምታውቁት በሕገ መንግሥታችንም ሆነ በመንግሥት አመራራችን የሚሻሻል ነገር ካለ ለማሻሻል እርምጃ ከመውሰድ መቆጠብ የለብንም። ከሕዝቡ ችሎታና ከኑሮው አቅም በላይ የሆነውን ነገር ደግሞ፤ አመቺ የሆነው ጊዜ እስኪደርስ ድረስ ከመጠበቅ በስተቀር ውጤት የማይሰጥ ሙከራ ማድረግ ጠቃሚ አይደለም። በእኛ ዕምነት ማናቸውም የአስተዳደር

ሥርዓት መሻሻል ያለበት፤ ሕዝቡ ከደረሰበት የኑሮ ደረጃ ጋር እየተመዘነ መሆን አለበት እንጂ፤ እንዲሁ በደፈናው ለፎርም እየታሰበ የሌላውን አገር አሠራር መቅዳት አያስፈልግም። ስለዚህ፤ እናንተን የምጠይቃችሁ ስለ አገራችን ጠቅላላ ሁኔታና ስለ እኛም አመራር የማታውቁት አዲስ ነገር ይኖራል ለማለት ሳይሆን፤ ለሕዝባችን ጠቃሚ የሚሆንና የውጭውንም ዓለም ነቀፌታ የሚገታልን መልካም ሐሳብ ከተገኘ፤ እርምጃ እንድንወስድበት አጥንታችሁ እንድታቀርቡልን ነው .... "

በዚያች በመጋቢት 11 ቀን 1939 ዓ.ም ጃንሆይ የመንግሥታቸውን አስተዳደር ለማሻሻል እስከዚህ ያሰቡበት ምክንያት ከምን የተነሣ እንደሆነ ለሦስቱም ዋና ዋና ባለሥልጣኖች ግልጽ አልሆነላቸውም ነበር። ሦስቱም ከላይ የተገለጸውን መምሪያ ተቀብለው ከአምሳለ ገነት የንጉሠ ነገሥቱ ጽሕፈት ቤት ከወጡ በኋላ፤ ወደ ገነተ ልዑል ቤተመንግሥት የእንግዶች ማረፊያ ሳሎን ሄደው፤ ምን ማድረግ እንደሚሻል እርስ በርሳቸው በሰፊው ተወያዩ። በመጨረሻው ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ባቀረቡት ሐሳብ፤ " .... ሦስታችንም በየበኩላችን የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት የሚሻሻለው በምንና ምን ጉዳዮች ላይ መሆኑን አጥንተን በተወሰነ ቀን በቀጠሮ ብንገናኝና ብንወያይበት ይሻላል .... " ስለአሉ፤ ሦስቱም በዚሁ ተስማምተው ተለያዩ።

በተቃጠሩበት ቀንና ሰዓት እንደ ኢ.ት.አቆ መጋቢት 18/1939 ሲገናኙ፤ ሦስቱም ባለሥልጣኖች በየበኩላቸው አጥንተው የነደፏቸው ሐሳቦች የሚከተሉት ነበሩ።

### ሀ/ ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው - ጠቅላይ ሚኒስትር

" .... እኔ እንደገባኝ ጃንሆይ የተጨነቁት ኢትዮጵያ የዘመኑን ሥልጣኔ ባለመከተል እጅግ ወደ ኋላ ቀርታለች እየተባለ በተለይ በአውሮፓ አገሮች ከሚገባ በላይ ፕሮፓጋንዳ ስለሚነዛብን፤ ይህንን ለማስታገሥ የሚያስችል አንድ ዓይነት የአስተዳደር መሻሻል ማድረግ ያስፈልጋል በማለት ነው። እስከዛሬ ድረስ እንደምናየው የአውሮፓ መንግሥታት እኛን ከመከታተልና በአገራችን ውስጥ የሚከናወኑትን ሥራዎች ሁሉ ከመቆጣጠር አቋርጠው አያውቁም። ጃንሆይ እንደተናገሩት በተለይ ከጠላት ወረራ ወዲህ ለአገር ሥልጣኔ የሚረዱ ብዙ ሥራዎች ተሠርተው ነበር። ከእነዚህ ውስጥ ዋነኛው የትምህርት መስፋፋት ነው። ይሁን እንጂ፤ ይህ ሁሉ ጥረት በአውሮፓውያኖቹ ዘንድ በቂ ነው ተብሎ አልተገመተም። ስለዚህ፤ ጃንሆይ የሚያደርጉት የአስተዳደር መሻሻል ቅደም ተከተሉ ምንና ምን መሆን እንደሚገባ ለማጥናት ቅድሚያ መስጠት ያስፈልጋል። ለዚህ በእኔ ሐሳብ፤ በአሜሪካ፤ በእንግሊዝና በፈረንሣይ መንግሥታት ዘንድ ነዋሪዎች የሆኑት የጃንሆይ የዲፕሎማቲክ እንደራሴዎች፤ ኢትዮጵያ በሥልጣኔ ለመራመድ የምትችለው በምን መንገድ እንደሆነ የእነዚህ አገሮች አስተያየትና ዕምነት ምንና ምኖች መሆናቸውን እያጠኑ፤ በሰፊ ራፖር እንዲያቀርቡልን ትዕዛዙ እንዲተላለፍላቸው ማድረግ የመጀመሪያው እርምጃችን መሆን ይገባዋል። እነዚህ የሚያስፈልጉን ጥናቶች ከደረሱን በኋላ፤ ጃንሆይ እንዳዘዙን እኛም ተሰብስበን ፍሬ ነገሮቹን እየመዘንን ለአስተዳደሩ መሻሻል ጠቃሚ የሆኑትን ሁሉ ለመምረጥና ቅደም ተከተሉን አስተካክሎ ለጃንሆይ ለማቅረብ ይመችናል። ከዚያ በፊት ግን፤ እኛ ብቻችንን ተወያይተን የምናቀርበው ሐሳብ በቂ ሊሆን አይችልም .... "

ለ/ አቶ መኩንን ሀብተወልድ - የእርሻ የንግድና የኢንዱስትሪ ሚኒስትር፤

" .... እኔ በበኩሌ አጥንቼ ይዤው የመጣሁት ሐሳብ፤ አሁን ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር ከተናገሩት የተለየ እንደሚሆን ይሰማኛል። በመሠረቱ ከጃንሆይ በተሰጠን መመሪያ ላይ እያንዳንዳችን የተለያየ ሐሳብ ቢኖረን የሚከፋ አይደለም። ይልቁንም በተለያዩ ሐሳቦች ላይ ስንወያይ ጠቃሚ ውጤቶችን ማምረት እንችላለን። .... እኔ ከልቤ እንደማስበው፤ የጃንሆይ መንግሥት የአስተዳደሩን ሥርዓት እንዲያሻሽል ሁላችንም የምንደግፈውና የምናምንበት ጉዳይ መሆን አለበት። ይሁን እንጂ፤ የሚደረገው የአስተዳደር መሻሻል ከሁሉ በፊት የኢትዮጵያን ሕዝብ ፍላጐትና ምኞት እንዲከተል እንጂ፤ ፈረንጆቹን ለማስደሰት እንዲሆን መታሰብ የለበትም ብዬ ስናገር፤ ተሳስተሃል ልትሉኝ ትችላላችሁ። በእኔ አስተያየት ፈረንጆቹ የምንላቸው የአውሮፓ መንግሥታት የኢትዮጵያን አመራር ፌዎዳል ነው እያሉ ከመንቀፍ ምንጊዜም ሳያቋርጡ እንደሚኖሩት ሁሉ፤ በአንድ ተአምር የነዳጅ ዘይት ከመሬታችን ፈልቆ ወይም የተለየ የማዕድን ሀብት አግኝተን፤ ዘመናዊውን ሥልጣኔ ለመቀበል ተዘጋጅተን ብንገኝ በቅናትና በተንኮል ከመከታተል በስተቀር፤ አይዟችሁ በርቱ ይሉናል ወይም ይረዱናል ብለን መጠበቅ የለብንም። በዚያ በመከራው ዘመን የፈረንጆቹን መንግሥታት ጨዋንትና ዳኘነት በሚገባ አይተናል። ነፃነታችን ከተመለሰም በኋላ በሰላም እንድንኖር እንዳልተፈለገ ሁላችንም እናስታውሳለን። ይህንን ሁሉ ችግር ለመወጣት የቻልነውም በእግዚአብሔር እርዳታና በጃንሆይ ጥንካሬ መሆኑን መርሳት የለብንም። ስለዚህም ነው፤ ቀደም ብዬ ስናገር የመንግሥታችንን አስተዳደር ለማሻሻል ከኢትዮጵያ ሕዝብ ፍላጐትና ምኞች ጋር እንዲስማማ ከማሰብ በስተቀር፤ ጠላቶቻችንን ለማስታገሥ ወይም ለማስደሰት በሚል መንፈስ መጨነቅ የለብንም ያልኩት። ..... አሁን ወደ ዋናው ጉዳይ ልመለስና በእኔ ጥናት፤ ጃንሆይ ለሚወዱት ሕዝባቸው ደህንነትና ዕድገት የሚያሻሽሉለት ብዙ ነገሮች ቢኖሩም፤ ለጊዜው ቅድሚያ የሚሰጣቸው ሁለት ዋና ዋና የሆኑ ጉዳዮች አሉ። እነዚህም አንደኛው የባለርስትንና የአራሹን ገበሬ ግንኙነት የሚመለከት ሲሆን፤ ሁለተኛው ደግሞ፤ የአገረ ገዥዎችንና የሚያስተዳድሩትን ሕዝብ ግዴታና መብት በሕግ መለየት ነው። እስከ ዛሬ ድረስ እንደአየነው ብዙዎቹ ባለርስቶች ጢሰኛ እየተባለ በሚጠራው ገበሬ ላይ ከሕግ ውጭ የሚፈጽሙት በደልና የሚያደርሱት ጉዳት እጅግ የከበደ መሆኑን መካድ አይቻልም። ሰብዓዊ መንፈስ የሌላቸው ባለርስቶች ገበሬውን ከሰፈረበት መሬት ላይ ጊዜውን ሳይመርጡ እነሱ እንደፈለጋቸው እየነቀሉ ያባርሯቸዋል። በዚህ ጊዜ ለነዚህ ድሆች የሚደርስላቸው የለም። እርግጥ ነው አንዳንዶቹ ባለርስቶች ከገበሬው ጋር በአበልጆነትም ሆነ በጡት ልጅነት እየተሳሰሩ በቤተሰብ መንፈስ ተስማምተው የሚኖሩ አሉ። ይሁን እንጂ፤ እነሱም ቢሆኑ በመካከላቸው አለመግባባት በተፈጠረ ጊዜ መንግሥት በዳኝነት የሚገላግልበት ሕግ ስለሌለ፤ ለሰላም ሕይወታቸው ዋስትና የላቸውም። ስለዚህ በእኔ አስተያየት ጃንሆይ አብዛኛው ሕዝባቸው የሰላም ኑሮ እንዲያገኝ አንድ ትልቅ ችግር ማስወገድ የሚችሉት፤ በባለርስቶችና ጢሰኛ እየተባሉ በሚጠሩት በገበሬዎች መካከል ያለው ግንኙነት በሕግ የተወሰነ እንዲሆን በማድረግ ነው። ይህ የሚወጣው ሕግ የባለርስቶቹንና የአራሾቹን ገበሬዎች መብት በየመልኩ የሚጠብቅ ስለሆነ፤ ከእርሻ የሚገኙትን ውጤቶች ሁሉ በይበልጥ ለማስፋፋት የሚያስችል ይሆናል ብዬ አምናለሁ። ቀደም ብዬ እንደጠቀስኩት የሚቀጥለው ትልቁ ጉዳይ፤ የአገረ ገዥዎችን የአስተዳደር ሥልጣን በሕግ ለይቶ መወሰን ነው።

አሁን ያለውን የአስተዳደር ሁኔታ ስንመለከት፤ ጃንሆይ " .... እናንተ ለሕዝብ ተሰጣችሁ እንጂ፤ ሕዝብ ለእናንተ እንዲያገለግል አልተሰጣችሁም .... " እያሉ መምሪያቸውን ቢያጠነክሩም፤ ብዙዎቹ ገዥዎች በየግዛታቸው ዘውድ ቀረሽ

ንጉሥ እየሆኑ፣ በሚያስተዳድሩት ሕዝብ ላይ ብዙ ግፍ እንደሚፈጽሙ ሁላችንም እናውቃለን። ለዚህ መድኃኒቱ "አገረ ገዥ" ማለት ምን ትርጉም እንዳለውና ኃላፊነቱንም የሚያከናውነው በምን መልክ እንደሆነ በጽሑፍ ተገልጾ በሕግ ሲወሰን ነው። አለበለዚያ ገዥዎች ሁሉ አሁን ባለው አሠራራቸው እንደአሰኛቸው የመግረፍም ሆነ የማሠር ሥልጣን ይዘው ከቀጠሉ፣ አንድ ጊዜ ሕዝቡ ከምሬቱ የተነሣ አድማ መትቶ መንግሥትን አላውቅም ከሚልበት ደረጃ እንዳይደርስ እጅግ ያሠጋል። ስለዚህ፣ ለየአውራጃው የሚሾሙት ገዥዎች ሥራቸውን ከመጀመራቸው በፊት የሕዝቡን መብት እያስከበሩ አስተዳደሩን የሚመሩበት የተግባር ምዕዳን (ሥርዓት) እንዲሰጣቸው ያስፈልጋል። ከጥቂት ዓመታት በፊት ወዳጄ ወንድሜ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና እኔ የአውራጃዎችን አስተዳደር በዘመናዊ መንገድ ለማሻሻል በቅድሚያ ከሕዝቡ ሕይወት ጋር ቅርበት ያላቸው ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች እንዲሠለጥኑ እርምጃ ወስደን ነበር። የሚያሳዝነው ይህንን በቅን መንፈስ ያሰብነውን ጉዳይ መሳፍንትና መኳንንት የቤተክህነት መሪዎችም ጭምር ስለተቃወሙት፣ ፍሬ ሳይሰጠ ቀረ። ከእንግዲህ ወዲህ ግን የምናቀርበው ሐሳብ በግርማዊ ንጉሠ ነገሥት መልካም ፈቃድ በአዋጅ የሚደነገግ ስለሆነ፣ በሥራ ላይ በሚውልበት ጊዜ ለሕዝቡ ትልቅ ደስታ እንደሚሆን አያጠራጥርም።

ክቡር ቢትወደድ ጠቅላይ ሚኒስትር
ክቡር ጸሐፊ ትዕዛዝ የጽሕፈት ሚኒስትር

እንደምታውቁት የአንድ አገር አስተዳደር መሻሻል ይደረግበት ሲባል፣ እኔ እንዳቀረብኩት ዓይነት በሁለትና በሦስት ጉዳዮች ላይ ይወሰናል ማለት አይደለም። የጃንሆይን መምሪያ ከተቀበልን በኋላ፣ ሁላችንም በየበኩላችን አስፈላጊ ነው የምንለውን ሐሳብ ነድፈን እንድንገናኝ በተስማማነው መሠረት፣ ይኸው በእኔ ዘንድ ያገኘኋቸውን ሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች አቅርቤያለሁ። ጃንሆይ በሰጡን መምሪያ እና በገለጹልን አስተያየት፣ የምናደርገው ጥናት ለኢትዮጵያ ሕዝብ ጠቃሚ ይሆናል ብለን የምናምንበትን ዘርዝረን እንድናቀርብ ስለሆነ፣ ምናልባት እኔ መሻሻል አለባቸው የምላቸው ሁለቱ ጉዳዮች ለውጭው አገር ፕሮፓጋንዳ መከላከያ በቂ አይደሉም ብላችሁ ታስቡ ይሆናል። እኔ ግን ቀደም ብዬ እንዳስረዳሁት፣ ለአገራችን አስተዳደር መሻሻል ጃንሆይ ለሚያደርጉት ጥረት፣ ቅድሚያ የሚሰጠው ለውስጣችን ጉዳይ እንጂ፣ ለውጭው ዓለም ፕሮፓጋንዳ መከላከያ መሆን የለበትም የሚለውን ዕምነቴን ከማጠንከር ወደ ኋላ አልልም። **የኔ ዕምነት መጀመሪያ የቤታችንን የውስጥ ችግር ካስወገድንና ትክክለኛውን መስመር ካስያዝን በኋላ፣ የአውሮፓን መንግሥታት ተቃውሞ መቋቋም እንችላለን የሚል ነው።** ስለዚህም በኢትዮጵያ ሕዝብ ጫንቃ ላይ ጉዳት የሚያደርሱትን የአገረ ገዥዎችንና የባለርስቶችን ጉዳይ በአስቸኳይ ለማሻሻል የሚመስለኝን ሐሳብ አቅርቤያለሁ።

<u>ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው፣</u>

" .... ዛሬ ለተሰበሰብንበት ጉዳይ የጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስን ጥናት ከማድመጣችን በፊት፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድ በተናገርከው ውስጥ በአንዳንዱ ጉዳይ ማዘኔን ሳልገልጽልህ ማለፍ አልፈልግም። የጠቅላይ ግዛትና የአውራጃ ገዥዎችን የአስተዳደር ሥልጣን ለማሻሻል በሚል አነጋገር ከጸሐፊ ትዕዛዝ ጋር ሆናችሁ ከጥቂት ዓመታት በፊት ያደረጋችሁት የምስለኔዎችና የጭቃ ሹሞች ስብሰባ ፍሬ ሊሰጥ ያልቻለው፣ በመሳፍንትና በመኳንንት ተቃውሞ ምክንያት ነው ብለሃል። ይህ በጣም የሚያሳዝን ነው። እስቲ ማን ይሙት ? ከመሳፍንቱም ሆነ

ከመኳንንቱ መካከል ማን ነው ? የተቃወማችሁና ያስባችሁትን ያደናቀፈባችሁ ? ተብላችሁ ብትጠየቁ መልስ እንደሌላችሁ የታወቀ ነው። በንጉሡ ነገሥቱ በወግና በሥርዓት የተሾሙትን አገረ ገዥዎች ወደ ጐን ትታችሁ፤ ከምስለኔዎችና ከጭቃ ሹሞች ጋር ስብሰባ ማድረጋችሁን ከመስማታችን በስተቀር፤ በምንና ምን ጉዳዮች ላይ እንደተነጋገራችሁ፤ በመጨረሻም ከምን ስምምነት ላይ ደርሳችሁ እንደተለያያችሁ፤ በእኛ በኩል የምናውቀው ነገር አልነበረም። ከሁሉ በፊት ልትወቀሱ የሚገባችሁ እናንተ ሁለታችሁ (ወልደ ጊዮርጊስና መኰንን) ነበራችሁ። የገዥዎችን ሥልጣን የሚመለከት፤ ይህን የመሰለውን ትልቅ ጉዳይ ስትጠነስሱትም ሆነ ከዳር ለማድረስ ስትሞክሩ፤ እኔም በጠቅላይ ሚኒስትርነቴ ሌሎቹም ጓደኞቻችሁ የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባሎች፤ እንኳንስ እንድንመክርበት ከሆነም በኋላ እንድናውቀው ፈቃዳችሁ አልሆነም። በመጨረሻውም ከምስለኔዎችና ከጭቃ ሹሞች ጋር ተነጋግራችሁ የተስማማችሁበት ጉዳይ ሊሰምር ያልቻለው፤ ጠቅላይ ገዥዎች በሕብረት ስለተነሡባችሁና ጠንክረው ስለተቃወሟችሁ መሆኑን ሁለታችሁም ደህና አድርጋችሁ ታውቃላችሁ። ነገር ግን፤ እውነተኛው ምክንያት ግልጽ ሆኖ እየታየ፤ ሌላ ሰበብ በመፍጠር የመሳፍንትና የመኳንንት ተቃውሞ ግባችንን አበላሸብን የሚል ሮሮ ማሰማቱ ለምን እንደሚጠቅማችሁ አልገባኝም። የሆነ ሆኖ ሁለታችሁም ሐሳባችሁን ማስተካከል ብቻ ሳይሆን ማረምም ይገባችኋል። አሁን ይኸ ጉዳይ አልፏል። እንደገና አንሥቶ መነጋገሩም አይጠቅምም። እኔም አስተያየቴን ለማስረዳት የተገደድኩት፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድ በተናገረው ስለአዘንኩ፤ እውነተኛው ምክንያት ተሸፍኖ እንዳይቀር ነው። አሁን፤ ወደጀመርነው ሥራ እንመለስና የጸሐፊ ትዕዛዝን ጥናት እናዳምጥ.... "

## ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፤

" .... ስለ አገር አስተዳደር መሻሻል፤ ጃንሆይ ባዘዙን መሠረት የእኔን ጥናት ከማቅረቤ በፊት፤ አቶ መኰንን ሀብተወልድንና እኔን በሚመለከት ጉዳይ ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር ስለተናገሩት፤ አስተያየቴን ማስቀደም እፈልጋለሁ። ክቡርነትዎ ለጠቅላይ ሚኒስትርነት ደረጃ ከመድረስዎ በፊት፤ በዲፕሎማሲ ሥራ የታላቁ መሪያችን የአፄ ኃይለሥላሴ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትር በመሆን፤ ሥልጣኔ እጅግ የገሰገሠበትን የአውሮፓውን ዓለምና በተለይም በእንግሊዝ አገር በመኖር ብዙ ነገሮችን የመመልከት ዕድል ስላገኙ፤ የዴሞክራሲን ትርጉምና ሥርዓት ከርስዎ የተሻለ የሚያውቅ ሌላ ሰው የለም ብዬ ብናገር ተሳስተሃል የሚለኝ አይኖርም። አሁንም ለእኔና ለአቶ መኰንን ባለፈው ጊዜ ስለአከናወንነው ሥራ የሚያስቡትንና የሚያምኑበትን በሰፊው የገለጹልን፤ በዴሞክራሲ ወግና ሥርዓት መሆኑን በሚገባ ተገንዝበናል። ስለዚህ፤ እኔም በበኩሌ ለክቡርነትዎ ደረጃና ሥልጣን ያለኝ አክብሮት ሳይዛነፍ፤ አሁን በተናገሩት ጉዳይ አስተያየቴን የምገልጽልዎ፤ የዴሞክራሲውን ሥርዓት በመተማመን መሆኑን እንዲያውቁልኝ አስቀድሜ እለምናለሁ።

..... አቶ መኰንን ሀብተወልድ ስለ መንግሥታችን አስተዳደር መሻሻል ጥናቱን ሲያቀርብ፤ በክቡርነትዎና በጓደኞችዎ መኳንንት ላይ አግባብ የሌለው ወቀሳ ለማቅረብ፤ ከዚህም በላይ ለደረሰብን ችግር ስሕተታችንን ሸፋፍኖ በመሳፍንትና በመኳንንት ላይ ለማሳበብ ፈልጎ አይደለም። እኔና አቶ መኰንን እየተግባባንና እየተረዳዳን በመሥራታችን የፖለቲካ ፓርቲዎች በመሆናችው ነው እየተባለ የሚነገርብንን ደህና አድርገን እናውቃለን። ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር

እንደሚያውቁት፣ የፖለቲካ ፓርቲ በአገራችን የለም። ስለዚህም፣ ለማንም ወገን ግልጽ ሆኖ መታየት ያለበት፣ እኔንና አቶ መኰንንን የሚያግባባንና የሚያቀራርበን ለታላቁ መሪያችን ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ታማኝነታችንና ለአገራችን ለኢትዮጵያ ያለን ተመሳሳይ የሆነ የአገር ፍቅር መሆኑን ነው። በተጨማሪም፣ ሁለታችንንም የሚያስማማን መሠረታዊው ጠባያችን፣ ሥርተን በምናስገኘው መልካም ውጤት አለመኩራታችን፣ ባለማወቅ በምናደርሰውም ስሕተት አለማፈራችን፣ ከታላቁ መሪያችን በተሰጠን ሥልጣን የምንሠራው የምናምንበትን፣ የምንናገረውም ትክክለኛውን ብቻ ስለሆነ ነው። ስለዚህ፣ በሥራችን ላይ የምናደርሰውን ስሕተት ለመሸፋፈን ወይም ደግሞ ሌላ ሰበብ ፈጥሮ ለመሸሽ ሐሳቡም ዕምነቱም የሌለን መሆኑ እንዲታወቅልን እንፈልጋለን።

...... ባለፉት ጥቂት ዓመታት ውስጥ በየአውራጃው ካሉት ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች መካከል፣ በቀለም ትምህርት የተሻሉትን መርጠን አቶ መኰንን እና እኔ አዲስ አበባ አስመጥተን የሰበሰብናቸው፣ የያዙትን ሥራና ኃላፊነት ለማሻሻል እንዲችሉ ለማስተማር እንጂ፣ የአገረ ገዥዎቹን ሥልጣን እንዲጋፉ ወይም ደግሞ ባለጋራ ሆነው እንዲያፈነግጡ አልነበረም። ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር እንደሚያውቁት ምስለኔዎችና ጭቃ ሹሞች፣ ከገባሩ ሕዝብ ኑሮ ጋር የተቀራረቡና አብረው የሚኖሩ በመሆናቸው፣ እነሱን በማሠልጠንና በማሻሻል በድሃው ሕዝብ ላይ ያለውን ከባድ ችግር በብዙ ረገድ ማቃለል ይቻል ነበር። አቶ መኰንን እና እኔም ይህንን ውጤት ለማግኘት እርምጃ ስንወስድ፣ ያላሰብነውና ያልጠበቅነው ተቃውሞ ስለገጠመን፣ በቅን መንፈስ የጀመርነውን ማቋረጥ ግዴታ ሆነብን። በዚህም ጊዜ፣ በእኛ ላይ ኃይለኛ የሆነ የአገረ ገዥዎች ተቃውሞ የደረሰብን ከአዲስ አበባ በክቡራን መኳንንት አነሣሽነት መሆኑን ተከታትለን ስለደረስንበት፣ ምሬታችንን በሚገባ ገልጸናል። ይህንንም ትናንት የተናገርነውን ዛሬም እንደግመዋለን። አስፈላጊ ከሆነ ደግሞ፣ ነገም ተነገ ወዲያም መላልሰን እናስረዳለን። በዚህ ጉዳይ ቀደም ሲል ክቡርነትዎ ሲናገሩ፣ " ... እስቲ ማን ይሙት ? ከመሳፍንቱና ከመኳንንቱ ውስጥ ማን ነው ? የተቃወማችሁና ሥራችሁን ያደናቀፈባችሁ ? ተብሎ ብትጠየቁ፣ መልስ እንደሌላችሁ የታወቀ ነው.... " ብለውናል። ይህ አነጋገር የእኛን ሰውነት ምን ያህል እንደሚነካና ምን ያህል እንደሚያሳዝን፣ ከክቡርነትዎ የተሠወረ አይደለም። እኛ የተናገርነውን አንክድም። ከክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር ጀምሮ የተቃወሙን እነ ማን መሆናቸውን ማስረጃው በእጃችን ስለሚገኝ፣ በማናቸውም ጊዜና ሰዓት አቅርበን ማስመስከር እንችላለን። " ..... በምስለኔዎችና በጭቃ ሹሞች ሥራ ጉዳይ፣ የመኰንን ሀብተወልድና የወልደጊዮርጊስ ፕላን በታላላቆቹ ያልተጠና እና ያልተመከረበት፣ ጃንሆይም ዘንድ ቀርቦ ያልተፈቀደ ስለሆነ፣ "እሻፈረኝ" ማለት ይገባችኋል ..... " ብላችሁ ከየጠቅላይ ገዥዎቹ ጋር የተለዋወጣችሁትን አስተያየት አግኝተን በሰነድ ይዘነዋል። ስለዚህ፣ አንደኛ/ አቅደነው ስለነበረው ፕላን፣ ሁለተኛ/ ፕላናችን የፈረሰው በምን ምክንያት እንደነበረ፣ የተናገርነው ሁሉ ትክክል ስለሆነ፣ ክቡርነትዎ እንደጠየቀን አቶ መኰንን እና እኔ፣ የምናርመው ሆነ የምናስተካክለው ነገር የለም። ወደፊት ጊዜና ታሪክ የሚሠራውን እየጠበቅን፣ ከመሠረታዊው አቋማችን ሳንዛነፍ፣ የእግዚአብሔር ፈቃዱ እስከሆነ ድረስ ግዳጃችንን እንቀጥላለን።

ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር፣

..... እንድንነጋገርበት በአጀንዳችን ላይ ባልተመዘገበ በዚህ ባለፈ ታሪክ፣ ሦስታችንም አስተያየታችንን ሰጥተንበታል። በመሠረቱ አጋጣሚ ሆኖ እንደዚህ

ተገላልጠን መነጋገራችንን ወድጄዋለሁ። ሆኖም በጀመርነው ከመቀጠል ሌላ የምናገኘው ጥቅም ስለሌለ፣ እዚሁ እደረስንበት ቦታ ላይ አቁመን፣ ወደተሰበሰብንበት ዋና ጉዳይ ብንመለስ የሚሻል ይመስለኛል። ውሳኔው የክቡርነትዎ ነው .... "

ቢትወደድ ጠቅላይ ሚኒስትር፣ አስቸጋሪ ከሆነ ፈተና ላይ ወደቁ። የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ጸሐፊ ትዕዛዝ እስከዚህ ጉድ ያፈላሉ ብለው አልጠበቁም። ወልደጊዮርጊስ፣ በአገር ግዛት ሚኒስትርነታቸው፣ ፖሊስና ፀጥታ በእጃቸው መሆኑን የዘነጉት ይመስላል። አጅሬ እንኳንስ መሳፍንትና መኳንንት የሚያካሂዱት የፖለቲካ ሥራ ይቅርና፣ የተራውንም ሰው ዕቅድና ሐሳብ ፈልፍለው የሚጨብጡ ስለሆኑ፣ እሳቸው ሳይደርሱበት ተሸፍኖ የሚያመልጥ አንዳች ነገር የለም። መኰንን ሀብተወልድ ባቀረቡት ሐሳብ ውስጥ፣ መሳፍንትና መኳንንት የምስለኔዎችንና የጭቃ ሹሞችን ጉዳይ ስለመቃወማቸው የጠቀሱትን፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩ የከረረ መልስ ባይሰጡበት ኖሮ፣ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ይህን ሁሉ ውርጅብኝ አይዘረግፉባቸውም ነበር። እንግዲህ ! ምን ይሻላል ? እንደምናየው፣ ሙግቱን መቀጠሉ ለቢትወደድ ጠቅላይ ሚኒስትር የሚያዋጣ አለመሆኑን ስለተረዱት፣ ከእነዚህ የፖለቲካ ወንድማማችነታቸውን ካጠነከሩት የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ባለሙሉ ሥልጣን ሚኒስትሮች ጋር በሰላም ለመገላገል የሚከተለውን ሐሳብ ሰጡ። " .... ጸሐፊ ትዕዛዝ በመጨረሻ በሰጠኸው ሐሳብ እስማማለሁ። አንድ ጉዳይ በአንድ ዓይነት ጆሮ ካልተደመጠ፣ በሚቀራረብ አስተሳሰብ ካልተመዘነ፣ ጊዜ ከመፍጀቱ በስተቀር መግባባት ሊገኝ አይችልም። አንተና አቶ መኰንን ሐሳባችሁን እና ዕምነታችሁን አስተባብራችኋል። የእኔ ከሁለታችሁም የተለየ ነው። ስለዚህ፣ ሁላችንም በየበኩላችን የሚመስለንን እና የምናምንበትን አቋም ይዘን፣ ወደ ታዘዝነው ሥራችን ብንሻገር የተሻለ ስለሚሆን፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ያንተን ጥናት እንድትሰጠን እጠይቃለሁ .... "

## ፕላን ፤ ወልደጊዮርጊስ

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስ ያደረጉት ጥናት፣ ከቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸውና ከአቶ መኰንን ሀብተወልድ እጅግ የተለየ ከመሆኑም በላይ፣ ሰፋ ያለ ማብራሪያ የያዘ ነው። በጽሕፈትና በአገር ግዛት ሚኒስትሩ አስተያየት ማሻሻል የሚያስፈልገው፣ እ.ኤ.አ በ1931 ዓ.ም የወጣውን የመጀመሪያውን የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ሳይሆን፣ የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት አሠራርና አፈጻጸም የተፋጠነ እርምጃ ለማድረግ በሚያስችል መልክ ማደራጀት ነው። በወልደጊዮርጊስ ዕምነት ጃንሆይ በፈቃዳቸው በ1931 ዓ.ም ለኢትዮጵያ ሕዝብ የሰጡት ሕገ መንግሥት፣ አገራችን አሁን ላለችበት ደረጃ በቂ መሆኑን በማረጋገጥ አስተያየታቸውን ከገለጹ በኋላ፣ አጥንተው ያቀረቡት አዲሱ ፕላናቸው በሚከተሉት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ የተመሠረቱ መሆናቸውን አስረዱ።

<u>ሀ/ ፓርላማ፣</u>

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የመጀመሪያው ሕገ መንግሥት ከታወጀበት እ.ኤ.አ ከ1931 ዓ.ም ጀምሮ እስከ ዛሬ ድረስ ሲሠራበት እንደቆየው፣ ፓርላማው የሕግ መወሰኛንና የሕግ መምሪያን ምክር ቤቶች የያዘ ተቋም ነው።

## የሕግ መወሰኛው ምክር ቤት አባሎች

ቀጥታ በንጉሠ ነገሥቱ የሚሾሙ ናቸው። እነዚህም በውጭ አገር ቋንቋ "ሴናተሮች" እየተባሉ የሚጠሩት ታላላቅ ሰዎች፤ በአገር ጉዳይ ያላቸው ኃላፊነት እጅግ ከፍ ያለ ስለሆነ፤ ንጉሠ ነገሥቱ የሚመርጣቸው ከመሳፍንትና ከመኳንንት፤ የራስ ወርቅ ካሠሩት ጠቅላይ ገዥዎችና በየአውራጃው ከታወቁት ባላባቶች መካከል መሆን አለበት። እነዚህ ታላላቅ ሰዎች በኃላፊነት ከሚያከናውኑት ተግባሮች መካከል ባጭሩ፤ የንጉሠ ነገሥቱ መንግሥት ለአገር ሥልጣኔና ልማት የሚያዘጋጃቸውን ሕጐችና ደንቦች፤ እንዲሁም ከታላላቅ የውጭ አገር መንግሥታት ጋር የሚያደርጋቸውን የፖለቲካና የኢኮኖሚ ስምምነቶች መርምሮ አስተያየት መስጠትና ማፅደቅ ነው።

ለእነዚህም ለከፍተኛ የአገር ጉዳይ ተመርጠው ለሚሾሙት ሴናተሮች፤ በመንግሥት በኩል ለመኖሪያቸው የሚሰናዳላቸው ዝግጅትና ለክብራቸው መጠበቂያ የሚደረግላቸው ሁሉ፤ እጅግ የላቀ ሆኖ መገኘት ይገባዋል። ይኸውም፤ የመኖሪያ ቤታቸውን፣ የማዕረግ ልብሶቻቸውንና ጌጦቻቸውን፣ አውቶሞቢሎቻቸውንና የክብር ጠባቂዎቻቸውን የሚመለከት ይሆናል። በጠቅላላው፤ የሕግ መወሰኛ ምክር ቤት አባሎች፤ በአገር ጉዳይ ያለባቸውን ከፍተኛ ኃላፊነት በመመዘን፤ የሚሰጣቸው ክብርና የኑሮ ደረጃ፤ በእንግሊዝ አገር እንደሚገኙት የሎርዶች ምክር ቤት አባሎች ጋር የሚመሳሰል እንዲሆን ማድረግ ያስፈልጋል።

## የሕግ መምሪያው ምክር ቤት አባሎች

እስከዛሬ ድረስ ሲሠራበት እንደቆየው፤ ሕዝቡ ራሱ በቀጥታ እንደራሴዎቹን ለመምረጥ ችሎታው እስከሚፈቅድለት ድረስ፤ መንግሥት በስሙ ሆኖ የሚያደርገው ምርጫ ለጊዜው መቀጠል አለበት። ሆኖም ሁለት ነገሮችን ማሻሻል ያስፈልጋል። ይኸውም፤ መጀመሪያ በሕዝብ ስም እንዲያገለግሉ የሚመረጡት መማክርቶች በአስተያየታቸውና በሥራ ልምዳቸው ከዚህ ቀደም ከነበሩት የተሻሉ እንዲሆኑ የተቻለውን ማድረግ ሲሆን፤ ቀጥሎ ደግሞ ከተመረጡ በኋላ ሥራቸውን ከመጀመራቸው በፊት፤ ኃላፊነታቸውንና ተግባራቸውን የሚመለከት የጥቂት ሳምንታት የተወሰነ የትምህርት ፕሮግራም ቢዘጋጅላቸው ይጠቅማል።

የመምሪያው ምክር ቤት፤ መንግሥት ለሕዝብ አስተዳደርና ለአገር ልማት ጥቅም እንዲውል በየጊዜው የሚያወጣቸውን በአንቀጾች የተጠናቀቁ ሕጐችንና ደንቦችን መርምሮ ከአስተያየት ጋር ለመወሰኛው ምክር ቤት ማሳለፍ የመጀመሪያ ተግባሩ ሲሆን፤ በሌላ በኩል ደግሞ፤ ምክር ቤቱ ራሱ በአባሎቹ አማካይነት ለሕዝብ ጥቅም የሚሰጡ ናቸው ብሎ የሚያምንባቸውን የሕግ ረቂቆች እያዘጋጀ ለመወሰኛው ምክር ቤት ማቅረብ ይችላል። ይህ መብት በሕገ መንግሥቱ አንቀጽ ውስጥ በግልጽ የተጠቀሰ ቢሆንም፤ እስከ ዛሬ ድረስ ጠቃሚና በቂ በሆነ መልክ አልተሠራበትም። ወደፊት ግን፤ የተመራጮቹ የአስተያየት ደረጃ እንዲሻሻል ከታሰበበትና ሕገ መንግሥቱ የሰጠው መብት እንዲሠራበት ከተደረገ፤ ለአገራችን ከፍ ያለ እርምጃ መሆን ይችላል።

## ለ/ መንግሥት፣

እንደሚታወቀው፣ ፓርላማው በፈረንጆቹ አጠራር "የሌጂስላቲፍ" ማለት የሕግ ማደራጃና ማጽደቂያ ተቋም ሲሆን፣ የአስፈጻሚውና የአስተዳዳሪው ክፍል ደግሞ፣ "መንግሥት" ይባላል። ይህንንም የሕግ አስፈጻሚና የአገር አስተዳዳሪነት ሥልጣን ያለውን መንግሥት የሚያቋቁሙትና ለየሥራው ዘርፍ የሚያስፈልጉትን ሚኒስትሮች፣ እንደራሴዎች፣ የሲቪልና የጦር ከፍተኛ ኃላፊዎች የሚሾሙት ንጉሠ ነገሥቱ ናቸው። እነዚህም የመንግሥት ባለሥልጣኖች የሚመረጡት፣ ከተማሩትና የዘመኑን ሥልጣኔ ለመከታተል ችሎታቸው ከሚፈቅደላቸው በዕድሜያቸውም ወጣት ከሆኑት ወገኖች መካከል መሆን አለበት። በዚህም አኳኋን፣ የተቋቋመው መንግሥት ቀጥታ ኃላፊነቱ ለንጉሠ ነገሥቱ ሲሆን፣ በተዘዋዋሪም ጉዳና ለፓርላማው ተጠሪ ይሆናል።

ቀደም ብዬ እንደገለጽኩት፣ ለፓርላማው ሕገ መንግሥቱ የሚሰጠው ኃላፊነት፣ የሕግ ማደራጀትንና ማጽደቅን ሲሆን፣ መንግሥት ደግሞ የአስፈጻሚነቱንና የአገሩን አስተዳደር ሙሉ ሥልጣን የሚቀበል ነው። በሁለቱም ወገኖች፣ ማለት በሌጂስላቲፉና በኤግዚኩቲፉ መካከል መግባባትና መተባበር እንዲኖር ከበላይ ሆነው የሚመሩት ንጉሠ ነገሥቱ ስለሆኑ፣ ያለ አንዳች ችግር የአገሪቱ የሥልጣኔ ዕድገትና ልማት በተፋጠነ ሁኔታ ሊገዝ ይችላል። ለአገሪቱ ሥልጣኔና ዕድገት መንግሥት ሕጉችና ደንቦች አዘጋጅቶ እንዲጸድቅለት ለፓርላማው በሚያቀርብ ጊዜ፣ የሕግ መምሪያው አባሎች በሕዝብ ስም የሚናገሩ ሲሆኑ፣ የሕግ መወሰኛው "ሴናተሮች" ደግሞ በአገሩና በዘውዱ ስም ሆነው አስተያየት የሚሰጡ ናቸው። ሁለቱም ምክር ቤቶች በየፊናቸው የሚጠይቋቸውን ማብራሪያዎች፣ ጉዳዩ የሚመለከተው ሚኒስትር ከፊታቸው ቀርቦ በአክብሮት ማስረዳት፣ የመጀመሪያው ግዳጁ ይሆናል። ይህን በመሰለው አሠራር፣ በሁለቱም ወገኖች (ማለት በሌጂስላቲፉና በኤግዚኩቲፉ) መካከል መግባባትና መተባበር ከተመሠረተ፣ የሚገኘው ውጤት የአገሪቱን የሥልጣኔ እርምጃ በይበልጥ እንደሚያፋጥነው ዕምነቴ የፀና ነው።

## ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር፣

ጃንሆይ ለሦስታችንም በሰጡን ትዕዛዝ መሠረት የበኩሌን ጥናት ሳደርግ፣ ለአገራችን አስተዳደር የፓርላማውንና የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት የኃላፊነት ድርሻ ከፋፍሎ አሠራሩንና አፈጻጸሙን ከማሻሻል በስተቀር፣ የተለየ መንገድ አላገኘሁም። ለብዙ ሰዎች አሁን ያለውን አስተዳደር ዘመኑ በሚጠይቀው መልክ ለማሻሻል ቀላል መስሎ ይታያቸዋል። አንዳንዶቹም እንደ እንግሊዝ አገር ለምን አይሆንም ? የሚሉ አሉ። እኔ በዚያ በመከራው የስደት ዘመን እንዳየሁት፣ ዛሬ በአለንበት ሰዓት ለኢትዮጵያ አስተዳደር እንደ እንግሊዝ አገር፣ ንጉሥ የታሪክና የባህል የበላይ ጠባቂ ሆኖ ይነግሣል፣ መንግሥት ደግሞ በፓርላማ ሕዝብ ቀጥታ ከመረጣቸው እንደራሴዎች መካከል በፖለቲካ ፓርቲ አሸናፊ የሆነው ይመረጣል፣ የሚለውን ሐሳብ ወስዶ መጠቀም ይቻላል ብዬ አላምንም። እንደ እንግሊዝ አገር መሆን እንችላለን ብሎ ማሰብ፣ አቅምን ካለማወቅ የተነሣ በሸንበቆ ላይ እንደሚገነባ ምኞት የሚቆጠር ይሆናል።

ምናልባት፣ ከእኛ የተለየና ጠቃሚ የሆነ ሐሳብ ይኖራቸዋል ብዬ በማሰብ፣ በሠለጠነው ዓለም ዩኒቨርሲቲ ተምረው የተመረቁትን ታናናሾች ወንድሞቻችንን፣

መኰንን ደስታን፣ አክሊሉ ሀብተወልድንና፣ ይልማ ዴሬሣን ስለ መንግሥታችን አስተዳደር መሻሻል አስተያየታቸውን እንዲሰጡኝ ጠይቄያቸው ነበር። አቶ መኰንን ደስታ እንደተለመደው እኛን ታላላቆቹን መዝለፍ ደስ ስለሚለው፣ "ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ፣ የአገር አስተዳደር እንዲሻሻል ትፈልጋላችሁ ብዬ ስለማላምን፣ አስተያየት የለኝም" አለኝ። አክሊሉና ይልማ ግን የገለጹልኝ አስተያየት ቁም ነገር ያለው ሆኖ ስለአገኘሁት፣ ልጠቅስላችሁ እወዳለሁ። በመጀመሪያ የተናገረው አክሊሉ እንዲህ አለ። " ..... አስተዳደሩን ለማሻሻል ጥናት እንድታደርጉ ያዘዟችሁ ጃንሆይ ስለሆኑ፣ የምታቀርቡት ሐሳብ የንጉሠ ነገሥቱን ሥልጣን የሚመለከት አይመስለኝም። ለምሳሌ፣ የጃንሆይ ሥልጣን ይቀነስ ቢባል፣ ሥልጣን የሚቀነሰው ለማን ለመስጠት ነው ? ለሚለው ጥያቄ መልስ ያስፈልጋል። እኔ እንደማየው በዛሬው ጊዜ ያለን ትልቁ ችግራችን፣ ሥልጣን ተጠቃልሎ በጃንሆይ እጅ መኖሩ ብቻ አይደለም። የመንግሥቱ አመራር በብዙ ቢሮክራሲ ተወጥሮ ሥርዓት የሌለውና የተተራመሰ በመሆኑ ይመስለኛል። ለዚህ መድኃኒቱ፣ በጃንሆይ በጐ ፈቃድ ጠቅላላ የሆነ የአድሚኒስትራሲዮን ሬፎርም ቢደረግ ነው። በዚህ መሠረት የእያንዳንዱ ሚኒስቴርና የአገር አስተዳደሩ ኃላፊነት እስከ ምን ድረስ እንደሆነ ተዘርዝሮ ሲለይ፣ በዚያው መጠን አስፈላጊው ሥልጣን ተከፋፍሎ መደልደል አለበት። ይህም የጃንሆይ ሥልጣን ተቀነሰ የሚያሰኝ ሳይሆን፣ የጃንሆይ ሥልጣን ለአፈጻጸሙ ረዳቶች እንዳገኘ የሚቆጠር ይሆናል ... " አለ። አቶ ይልማ ዴሬሣ ወዲያው ቀጠለና " .... አክሊሉ በተናገረው እስማማለሁ። በተጨማሪ የማቀርበው ሐሳብ፣ ከአድሚኒስትሬሽኑ ሪፎርም ጋር፣ የሌጂስላቲፍ ሥልጣን አለው የሚባለውን ፓርላማውንና ኤግዜኩቲፍ የሆነውን የመንግሥቱን ሥልጣን በየመልኩ ለይቶ በማስቀመጥ በትክክል እንዲሠራበት ቢደረግ፣ አገራችንን ወደ ዴሞክራሲ አስተዳደር የሚመራ ትልቅ ጉዳና ሊባል ይችላል .... " አለ።

እዚህ ላይ እንደምታዩት የእነዚህ የሁለቱ ወጣት ሚኒስትሮች አስተያየት እኔ ከነደፍኩት ሐሳብ ጋር የሚስማማ ሆኖ ስለአገኘሁት ደስ ብሎኛል። አስተዳደሩን ማሻሻል የሚያስፈልገው፣ አሠራሩንና አፈጻጸሙን ነው እንጂ፣ ሕገ መንግሥቱን ወይም የንጉሠ ነገሥቱን መንግሥት አቋም አይደለም። የውጭው አገር ጋዜጦች በየጊዜው ስለአገራችን የሚጽፉትን ስንመለከት፣ ስለ መንግሥታችን አሠራር የሚተቹን በሁለት ጉዳዮች ላይ ነው። ፩ኛ/ በፓርላማው የሕዝብ እንደራሴዎች የሆኑት የመምሪያው አባሎች ሕዝብ በራሱ ፈቃድ የመረጣቸው ሳይሆኑ፣ መንግሥት በሕዝብ ስም ሆኖ የሚደለድላቸው ስለሆኑ፣ የዴሞክራሲን ሥርዓት አልተከተለም በማለት ነው። ፪ኛው/ በመንግሥቱ ካቢኔ ውስጥ ንጉሠ ነገሥቱ ራሳቸው እንደ ጠቅላይ ሚኒስትር ሆነው በሙሉ ሥልጣን የሚሠሩ በመሆናቸው፣ ይህ የጠቅላይ ሚኒስትር ቦታ ለምን ተፈጠረ ብለው ይጠይቃሉ። ከዚህም ጋር አያይዘው የጽሕፈት ሚኒስትር የተባለው ቦታ በየትኛውም አገር የሌለ በመሆኑ ይገረማሉ። በኢትዮጵያ ያለው የጽሕፈት ሚኒስትሩ ሥልጣን በሌሎቹ አገሮች የሚሠራበት የመሪው ሼፍ ደ ካቢኔ (Chef DE Cabinet) የሚባለው ዓይነት መሆኑን እስከ ዛሬ አልተረዱትም። እንደ እውነቱ ከሆነም፣ በትክክል የሚያስረዳቸው አላገኙም። የጠቅላይ ሚኒስትሩን አስፈላጊነት ግን፣ ለውጭው ዓለም ብቻ ሳይሆን፣ ተግባሩ ምን እንደሆነ ለአገር ውስጥም ማብራራቱ ጠቃሚ ይሆናል። ይኸውም፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ዋናው ኃላፊነቱ የሚኒስትሮች ምክር ቤትን በሊቀመንበርነት መምራትና የሚኒስትሮቹን ሥራ ማስተባበር ነው። በሌላው ረገድ፣ በየጊዜው ከንጉሠ ነገሥቱ የሚሰጠውን ትዕዛዝ እየተቀበለ በየመልኩ ኃላፊነቱን ማከናወን ስለሆነ፣ አሁን ባለንበት ሁኔታ ለጊዜው ከዚህ የሚለወጥ ነገር

አይኖርም። በፓርላማ ስለ ሕዝብ እንደራሴዎች ምርጫ የተባለውን ቀደም ብዬ ከገለጽኩት የምጨምረው የለም። የሕዝቡ አስተሳሰብና አኗኗር ሲሻሻል፣ የንጉሠ ነገሥቱ የመጀመሪያ እርምጃ ሕገ መንግሥቱን አሻሽሎ ሕዝቡ እንደራሴዎቹን በቀጥታ እየመረጠ ወደ ፓርላማ እንዲልክ ማድረግ ነው። ይህንንም ወደፊት ለመፈጸም ጃንሆይ እጅግ ያሰቡበት ጉዳይ ስለሆነ፣ ረዥም ጊዜ የሚወስድ አይመስለኝም።

**ክቡር ጠቅላይ ሚኒስትር፤**

እኔ በበኩሌ ለአገራችን አስተዳደር መሻሻል አስፈላጊዎች የሚመስሉኝን ዋና ዋና ጉዳዮች ዘርዝሬአለሁ። ከእኔ በፊት አቶ መኰንን ሀብተወልድ ያጠናውን ሐሳብ ሲገልጽ፣ ሁለት ዋና ዋና የሆኑ ዓቢይ ጉዳዮች ለመሻሻል ቅድሚያ እንዲሰጣቸው አስረድቶናል። እነዚህም:- 1ኛ/ የአገረ ገዥዎች የአስተዳደር ሥልጣን በሕግ ተዘርዝሮ የተወሰነ እንዲሆንና የሕዝቡ መብት እንዲጠበቅ፣ 2ኛ/ በባለ ርስትና ጢሰኛ በተባለው ገበሬ መካከል ያለው ግንኙነትና የሚደረገው ውል፣ የሁለቱንም ወገኖች መብት በትክክል የሚለይ ሕግ እንዲዘጋጅ፣ ሲል ያቀረባቸው ሐሳቦች እጅግ ጠቃሚዎች ስለሆኑ፣ ለጃንሆይ በምናዘጋጀው ራፖር ላይ እንዲገቡ አሳስባለሁ።

ከዚህ በላይ በዝርዝር እንደታየው፣ የወልደጊዮርጊስ ጥናት በሐሳቡም ሆነ በአቀራረቡ ከጠቅላይ ሚኒስትሩና ከመኰንን ሀብተወልድ እጅግ የተለየ ነው። ጸሐፌ ትዕዛዝ ስለ ሴናተሮቹ አመራረጥና ስለሚሰጣቸው ክብር ያቀረቡት ዝርዝር ሐሳብ የሚያመለክተው፣ በንጉሠ ነገሥቱ ዙሪያ ቦታ ይዘው በአማካሪነት የምንሰጠው አስተያየት መደመጥ አለበት እያሉ ለመንግሥት አመራር እንቅፋት የሆኑትንና፣ ጠቅላይ ገዥዎችም ሆነው እየተሾሙ፣ በፊውዳላዊው ሥርዓት በሕዝብ ላይ ግፍ የሚፈጽሙትን መሳፍንትና መኳንንት፣ **እጅግ የተከበረው የትልቁ የሕግ መወሰኛ ምክር ቤት አባሎች ሆናችኋል ብሎ በነጋሪት አዋጅ በማሾም፣ ከመንግሥት ሥራ ውስጥ እንዳይገቡ ለማድረግ ነው።** መሳፍንትና መኳንንት እጅግ ያማረ መኖሪያ ቤት እየተዘጋጀላቸው፣ ከሌላው ሁሉ የተለየ በሆነው የክብር ልብሶቻቸው ላይ በኒሻኖችና በጌጣጌጦች እየተንቆጠቆጡ፣ በካዲላክ አውቶሞቢል እየተንፈላሰሱ እጅግ የተመቸ ሕይወት ሲያገኙ፣ ለአገር ዕድገትና ሥልጣኔ የሚደክሙትን ሚኒስትሮችና ሠራተኞች ለማስቸገር ጊዜ አይኖራቸውም ብለው፣ ጸሐፌ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ከልባቸው አስበዋል። **እነሱን ፀጥ ለማሰኘትና ሰላም ለማግኘት፣ ከመንግሥቱ ቋት ምንም ያህል ወጭ ቢደረግ፣ ከጉዳቱ ይልቅ ጥቅሙ የሚያመዝን ይሆናል ሲል ወጣቱ የገንዘብ ሚኒስትር ይልማ ዴሬሣ ድጋፉን ሰጥቶኛል ብለው ተደስተዋል።**

አጅሬ ወልደጊዮርጊስ ! ዘዴኛ በሆነው የፖለቲካ ጥበባቸው፣ ስለ ሴናተሮቹ ክብርና ምቹ ሕይወት ያሰቡት ሁሉ መሳፍንትንና መኳንንትን የሚያረካ እንጂ፣ የሚያሳዝን አይደለም። እንዲያውም የታሰበውን ሁሉ ንጉሠ ነገሥቱ ካጸደቁት፣ መሳፍንትና መኳንንት ሹመቱን እየተሻሙ ለመቀበል ጊዜ አይወስዱም። የወልደጊዮርጊስ ፕላን እንዲሠራበት ከተደረገ፣ የብዙዎች አገረ ገዢዎችና የአንዳንድ ሚኒስቴር ቦታዎች ስለሚለቀቁ፣ የተማሩትንና የዘመኑን ሥልጣኔ የሚከታተሉትን ሰዎች እየመረጡ ለመተካት ይመቻል ማለት ነው። በወልደጊዮርጊስ ምኞት <u>ያን ጊዜ ነው</u> በማናቸውም መስክ ፈጣንና ቀልጣፋ የሆነውን ዘመናዊ አስተዳደር **ለመመሥረትና የጨዋ ልጅ የድሃ ልጅ፣ የሚባለውን ልዩነት አጥፍቶ፣ ሁሉም የአንዲት ኢትዮጵያ ልጆች መሆን የሚችሉት !**

የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትር ፕላናቸውን አቅርበው አስተያየታቸውን ሲደመድሙ፣ ቢትወደድ ጠቅላይ ሚኒስትርና መኰንን ሀብተወልድ አድናቆታቸውንና የጋለ ደስታቸውን ገለጹላቸው። አቶ መኰንን፣ " ..... ጸሐፊ ትዕዛዝ ብዙ ጥናት አድርጉ ያቀረበው ሐሳብ፣ በቀጥታ ለጃንሆይ እንዲቀርብ ከማድረግ በስተቀር፣ በበኩሌ ይሻሻል ወይም ይጨመርበት የምለው የለኝም ..... " አሉ። ጠቅላይ ሚኒስትሩም በበኩላቸው፣ " .... ጸሐፊ ትዕዛዝ ያደረግከው ጥናት ጃንሆይ የሚፈልጉትን በሙሉ ያጠቃለለና በሰፊው የሚያብራራ ስለሆነ፣ አቶ መኰንን ሀብተወልድ እንደ አሳሰበው፣ ይኸው ጥናት ምንም ሳይነካና ምንም ሳይጨመርበት ለጃንሆይ መቅረብ አለበት። ሁለታችሁም ጸሐፊ ትዕዛዝና አቶ መኰንን ደህና አድርጋችሁ እንደምታውቁት፣ ጃንሆይ ስለ አስተዳደር መሻሻል ጥናት እንዲደረግ መምሪያ ሲሰጡ፣ አስፈላጊውን የምታዘጋጁት እናንተ ሆናችሁ፣ እኔ በተቀዳሚነቴ እናንተ የምትሠሩትን ለማስተባበርና በእናንተ ስም ዝግጅቱን ለጃንሆይ ለማቅረብ ነው። ስለዚህ፣ ጸሐፊ ትዕዛዝ ያሰናዳኸውን ሁላችንም የተስማማንበት ስለሆነ፣ ለእኔ ስጠኝና በእስቸኳይ ለጃንሆይ አቀርብላቸዋለሁ ... " አሉ። በዚህ ጊዜ ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ፣ " .... ይህ በእጄ የጻፍኩት ማስታወሻ በደህና ጸሐፊ ይገልበጥና ሦስታችንም ፈርመንበት ለጃንሆይ ቢቀርብ ይሻላል .... " አሉ። ጠቅላይ ሚኒስትሩ አልተስማሙም። " .... ስማኝ ጸሐፊ ትዕዛዝ ! ጃንሆይ ያንተን ብዕር በማንበብ ብዙ ልምድ አላቸው። ከዚህም በላይ የፊደል አጣጣልህ ሁሉ ግልጽ ስለሆነ፣ በጣም ይወዱታል። ገልባጭ ቁም ጸሐፊ አያስፈልግም። እንዲያውም፣ ጸሐፊ ሲፈለግ ምሥጢር ማባከን ይሆናል። ስለዚህ፣ ለእኔ ስጠኝና እኔው ራሴ ዛሬ ማታ ለጃንሆይ አቀርብላቸዋለሁ .... " ብለው፣ ፕላኑን ከወልደጊዮርጊስ እጅ ወሰዱት።

## መጨረሻው ምን ይሆን ?

ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስና አቶ መኰንን ሀብተወልድ፣ ካሁን ካሁን ጃንሆይ ጠርተውን በቀረበው ፕላን ላይ ንግግር ይደረግበታል ብለው ሲጠባበቁ፣ ሳምንታት አለፉ። በመጨረሻው ያ የደከምንበት ጉዳይ ከምን ደረሰ ? ብለው ጸሐፊ ትዕዛዝ ሲጠይቋቸው፣ የጠቅላይ ሚኒስትሩ መልስ እጅግ አስገረማቸው። " ..... እኔ በበኩሌ አቅርቤያለሁ። ጃንሆይ መልስ ያልሰጡት፣ ምናልባት የሚጥማቸው ሐሳብ ባለማግኘታቸው ወይም ደግሞ ባለመስማማታቸው ይሆናል .... " አሏቸው። ይህም ቢሆን፣ ጃንሆይ ! በልማዳቸው አንድ ሐሳብ በጽሑፍ ቀርቦላቸው መልስ ሳይሰጡ የቀሩበት ጊዜ የለም። ጸሐፊ ትዕዛዝ፣ ካቶ መኰንን ሀብተወልድ ጋር ሲመካከሩ፣ ያለ ጥርጥር በጀርባችን አንድ ተንኮል ተሠርቶብናል በማለት፣ ከፍ ያለ ቅሬታ ተሰማቸው። ጸሐፊ ትዕዛዝ ወልደጊዮርጊስ ኋላ ቆይተው ያንኑ ቀሪ ሳይዙ የጠፋውን ዶክመንት እንደገና በጽሑፍ ለማስፈር ሞክረው ነበር። በልማድ እንደሚታወቀው፣ አንድ ሐሳብ በብዙ ጥረት ከአዕምሮ ተጨምቆ በጽሑፍ ከሠፈረ በኋላ፣ ቀሪ ሳይያዝለት ዋናው ሰነድ ከጠፋ፣ መልሶ እንደነበረው አድርጉ ለመጻፍ እጅግ ያስቸግራል። ሆኖም ወልደጊዮርጊስ በዚሁ ማስታወሻቸው ላይ እንደገለጹት፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ዋናውን ዶክመንት ወስደው፣ ለጃንሆይ የተሳሳተ ትርጉምና አስተያየት በመስጠት ጉዳዩ ተነሥቶ ንግግር ሳይደረግበት ተድበስብሶ እንዲቀር አድርገዋል በማለት፣ ቅሬታቸውን ተናግረዋል።

አንዳንድ ሰዎች፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩ የወልደጊዮርጊስን የመንግሥት አስተዳደር ማሻሻያ ፕላን እስማማበታለሁ ብለው ቃል ከሰጡ በኋላ፣ በመጨረሻው



ክቡር ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው፤ ጠቅላይ ሚኒስትር

እንዴት ተቃዋሚ ይሆናሉ ? የሚል ጥያቄ ሲያቀርቡ ይችላሉ። በዚህ መጽሐፍ ደራሲ አስተያየት፣ ቢትወደድ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ሐሳባቸውን ለውጠው ተቃዋሚ ቢሆኑ፣ የሚያስደንቅ ሊሆን አይችልም። የወልደጊዮርጊስ ፕላንና እንዲሁም ከመኰንን ሀብተወልድ የቀረበው ሐሳብ፣ ትክክለኛው መልዕክቱ ምን እንደሆነ ቢመረመር፣ መሳፍንትና መኳንንት ለኢትዮጵያ ሕዝብ አስተዳደር መሻሻልና የሥልጣኔ ዕድገት ዋናዎቹ እንቅፋቶች በመሆናቸው፣ በተቻለ መጠን እነሱን ከሥልጣን ማራቅ በጣም አስፈላጊነቱን በግልጽ የሚያሳይ ነው። እንግዲያውስ ! ቢትወደድ መኰንን እንዳልካቸው ማን ናቸው ? ብሎ መጠየቅ ያስፈልጋል። ትውልዳቸው እንደ ታላላቆቹ መሳፍንት እንደነ ልዑል ራስ ካሣ ደረጃ የሚቆጠር ባይሆንም፣ የልጅ ኢያሱ ሞግዚት በመሆን መላ ኢትዮጵያን ሲያስተዳድሩ የነበሩት የራስ ተሰማ ናደው ቤተሰብ በመሆናቸውና፣ ቀጥሎም የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን የወንድም ልጅ ልዕልት የሻሸ ወርቅ ይልማን በማግባታቸው፣ መኳንንትነታቸው የሚያጠራጥር አይደለም። ስለዚህ ! መሳፍንትንና መኳንንትን ከአስተዳደር ሥልጣን ለማግለል ፕላን ከሚነድፉት ከወልደጊዮርጊስና ከመኰንን ሀብተወልድ ጋር፣ የአዲስጌው አባላት እንዴት ተባባሪ መሆን ይችላሉ ? .... ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም ቢሆኑ፣ በኢትዮጵያ ሥልጣኔን ለማስፋፋት ለሚያደርጉት ጥረት፣ መሳፍንትና መኳንንት ስለማይመቿቸው ከሥልጣን መራቃቸውን ቢፈልጉትም፣ የወልደጊዮርጊስንና የመኰንን ሀብተወልድን ሐሳብ በመጋረጃ ውስጥ ካልሆነ በስተቀር በይፋ መቀበል አይችሉም። ወልደጊዮርጊስና መኰንንም የተቃውሞ አስተያየታቸውን በተወሰነ ክልል ውስጥ አጋጣሚ ዕድል ባገኙ ቁጥር ይገልጻሉ እንጂ፣ አደባባይ ወጥተው ለሕዝብ ለማስረዳት ከሚችሉበት ደረጃ አልደረሱም። በዚያን ጊዜ በኢትዮጵያ የመሳፍንትና የመኳንንት አቅም ገና አልተዳከመም።

የጽሕፈትና የአገር ግዛት ሚኒስትሩ፣ ይህ የደከሙበት የአገር አስተዳደር ማሻሻያ ዶክመንት፣ በጠቅላይ ሚኒስትሩ ተወስዶ የት እንደደረሰ ባለመታወቁ ሲያሳዝናቸው፣ በሌላ በኩል ደግሞ ንጉሠ ነገሥቱም የሰጠናችሁን መምሪያ ከምን አደረሳችሁት ? ብለው አለመጠየቃቸው የበለጠ አስገርሟቸዋል። በዚህ ጉዳይ በጻፉት የግል ማስታወሻቸው ላይ፣ ወልደጊዮርጊስ የገለጹት አስተያየት በታሪክ ሊጠቀስ የሚገባው ነው። " .... ይህን ከቁም ነገር ገበታ ላይ ሳይደርስ የት ወድቆ እንደቀረ ያልታወቀውን ዶክመንት፣ በመኖሪያ ቤቴ በጽሕፈት ጠረጴዛዬ ላይ ለብዙ ሰዓት አቀርቅሬ፣ ሐሳቤን ጨምቄ ባለኝ አቅም የለፋሁበት ሥራ ለመሆኑ እግዚአብሔር ምስክሬ ነው። ይህ ሁሉ ልፋት ለራሴ ወይም ለግል ሰው ጥቅም ሳይሆን፣ ለአገሬ ሕዝብ መልካም አስተዳደር በመጨነቅ ነበር። ቅዱስ ዳዊት "ወይፈድዮ ለኩሉ በከመ ምግባሩ እንዳለው፣ መልካም ለሠራ መልካም ይደረግለታል። ክፉም ለሠራ ዋጋውን ያገኛል ... " በሚል ጥቅስ መራራ ስሜታቸውን ደምድመዋል።